# ምዕራፍ ፩

## ጸሐፊ ትእዛዝ ወልደጊዮርጊስ በአውሮፖ ጉዞ ላይ

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ረዥሙን የአሜሪካ ጉብኝታቸውን ፈጽመው ሐምሌ 27 ቀን 1946 ዓ.ም አዲስ አበባ ከተመለሱ በኋላ፣ በጽሕፈትና በፍርድ ሚኒስትራቸው በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ላይ ቀዝቀዝ ያለ ሁኔታ ማሳየት መጀመራቸውን ብዙዎቹ የቤተመንግሥቱ ታላላቅ ሰዎች ተመልክተዋል።

ወልደጊዮርጊስም በበኩላቸው በቀን ማስታወሻቸው ላይ እንዳሰፈሩት፣ ከጃንሆይ ጋር የነበራቸው ያ ዘወትር ፀሐይ የማይለየው ግንኙነታቸው ከአሜሪካ ጉዞ መልስ፣ ከአውሮፓው ጉዞ ጥቂት ቀናት በፊት ዳመና ጥሎበት እንደታያቸው ጠቅሰዋል። በተጨማሪም ንጉሠ ነገሥቱ ከልማዳቸው ውጭ ጠቅላይ ሚኒስትሩን ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸውን የአገር ግዛት ሚኒስትሩን፣ ራስ አበበ አረጋይን የገንዘብ ሚኒስትሩን፣ አቶ መኰንን ሀብተወልድን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩን፣ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድንና በዚያን ጊዜ የየረርና ከረዩ አውራጃ ገዥ የነበሩትን ግራዝማች ሣህሉ ድፋዬን (ኋላ ደጃዝማች) በየተራ እየጠሩ ለረዥም ጊዜ በቆይታ አነጋግረዋቸዋል። ይኸንንም የሚያደርጉት በወልደጊዮርጊስ ላይ ዓድማ ለማስመታት ነው ተብሎ ከአንዳንድ የቤተመንግሥት ኃላፊዎች ከሆኑት ወዳጆቻቸው ለጸሐፊ ትዕዛዝ ተነግሯቸው ነበር።

ይሁን እንጂ፣ ወልደጊዮርጊስ ራሳቸው በጥርጣሬ በደረሱበትም ሆነ ወይም ከቅርብ ወዳጆቻቸው በሰሙት ተመሥርተው፣ ከነበረው ባሕርያቸው ለጊዜው አንዳች ለውጥ ለማሳየት አልፈለጉም። ለምሳሌ፣ በጣም የሚወዷቸው አክሊሉ ሀብተወልድ በራሳቸው ላይ ዓድማ ከሚጐነጉኑት ሰዎች አንዱ ናቸው ተብሎ ቢነገራቸውም፣ በማናቸውም ጉዳይ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ የሚሰጡትን ድጋፍ አላቋረጡም። ለዚህም አንድ ማስረጃ ቢቀርብ የሚበቃ ይሆናል።

"የኤርትራ ጉዳይ" በተሰኘው መጽሐፍ ክፍል 6 ምዕራፍ 13 ላይ በሰፊው እንደተገለጸው፣ የኤርትራ ቺፍ ኤግዜኩቲፍ የነበሩት ደጃዝማች ተድላ ባይሩ መስከረም 1 ቀን 1947 ዓ.ም ባደረጉት ንግግር፣ " ... **ያገሬ የመረብ ምላሽ ሕዝብ ከእናት አገሩ ከኢትዮጵያ ጋር በፌዴሬሽን ከማደር ይልቅ፣ ፍጹም የሆነ ውሕደት እንዲደረግ ቢመርጥ ለደስታዬ ወሰን አልሰጠውም ነበር** ... " የሚል ቃል ወረወሩ። ይህ ንግግር ግቡ ምን እንደሆነ ለማወቅና በዚህም ጉዳይ ላይ የንጉሠ ነገሥቱ አቋም ምን መሆኑን ለመረዳት፣ በአዲስ አበባ ያሉት የአሜሪካና የአውሮፓ መንግሥታት አምባሳደሮች የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ማብራሪያ እንዲሰጧቸው ጠየቁ። ዲፕሎማቶቹ ይህን ጥያቄ ያቀረቡት፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት የኤርትራን ፌዴሬሽን ለማፍረስ ያስባል ብለው በመጠራጠር ስለሆነ፣ አክሊሉ ሀብተወልድ ከምክትላቸው ከብላታ ዳዊት ዕቁባእግዚእ ጋር በመመካከር በፍጥነት መልሱን መስጠት አስፈላጊ ሆኖ አገኙት። " ... የኤርትራው ቺፍ ኤግዜኩቲፍ



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እንግሊዝን በኦፊሲየል ሲጐበኙ፤
ንግሥት ኤልሣቤጥ በክብር ሠረገላ እንደተቀበሏቸው፤



ጠቅላይ ሚኒስትር ዊንስተን ቸርችል
ንጉሠ ነገሥቱን ሲቀበሉ፤

ባደረጉት ንግግር፤ ፌዴሬሽኑ ቢፈርስ ምን ያህል ደስ እንደሚላቸው ምኞታቸውን ገለጹ እንጂ፤ የኤርትራ ፓርላማ ተነጋግሮበት እንዲወስን ያቀረቡት ሐሳብ የለም። በመሠረቱ የኤርትራ የፌዴሬሽን አስተዳደር እንዲሻሻል ወይም እንዲሰረዝ ለጉዳዩ አወሳሰን ኃላፊዎቹ ራሳቸው ኤርትራውያኖቹ ናቸው እንጂ፤ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት አለመሆኑ መታቅ አለበት ... " በሚል ቃል የፕሮቶኮሉ ሹም፤ ልጅ እንዳልካቸው መኰንን ለየአምባሳደሮቹ እንዲያስረዱ ተደረገ። የሀ መግለጫ ለውጭ አገር ጋዜጠኞችም ስለተዳረሰ፤ በቢ.ቢ.ሲ እና በጣልያን ራዲዮ በሰፊው ተወራ።

የኤርትራው ቺፍ ኤርዜኩቲፍ፤ ፌዴሬሽኑ ቢፈርስና ከእናት አገር ከኢትዮጵያ ጋር ውህደት ቢደረግ ምን ያህል እንደሚያረካቸው ያላቸውን ከፍተኛ ፍላጐት በመግለጽ ያደረጉትን ንግግር የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አክሊሉ አራክሰው ለውጭ አገር መንግሥታት እንደራሴዎች መግለጫ ሰጥተዋል በማለት፤ በኤርትራ ያሉት የአንድነት ወገኖች እጅግ ማዘናቸውን ለጃንሆይ በቴሌግራም አመለከቱ። ንጉሠ ነገሥቱም የውጭ ጉዳይ ሚኒስትራቸው በችኮላ ይህን መግለጫ በማውጣታቸው ከተቆጡ በኋላ፤ አንድነቶች እንዳመለከቱት፤ ተድላ ባይሩ ያደረጉት ዲስኩር ጠቃሚነቱ እስከ ምን እንሆነ ለመወያየት፤ በአምሳለ ገነት ጽሕፈት ቤታቸው ከፍተኛውን ስብሰባ አደረጉ። ... የተድላ ባይሩ ዲስኩር የምኞት መግለጫ እንጂ፤ እርምጃ የሚወሰድበት ሐሳብ አለመሆኑን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ በሰፊው ካስረዱ በኋላ፤ የኤርትራ ፌዴሬሽን እንዳይፈርስ ማቆየት ለንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ጠቃሚ መሆኑን በገለጹ ጊዜ፤ በመጀመሪያ ጃንሆይ፤ ቀጥሎ ራስ ካሣ፤ ከዚያም በተከታታይ የሐረሩ መስፍንና ጠቅላይ ሚኒስትሩ ቢትወደድ መኰንን ከፍ ያለ የወቀሳ ትችት ሲያወርዱባቸው፤ ከጐናቸው ቆመው የተሟገቱላቸው ወልደጊዮርጊስ ብቻ ነበሩ። የኤርትራ ፌዴሬሽን ዓለም የሚቀበለውን ሕግና ሥርዓት ሳይከተል፤ በአንድ ሰው ዲስኩር ሊፈርስ እንደማይችልና ከዚህም በላይ የፌዴሬሽኑ መፍረስ ለግርማዊነትዎ መንግሥት ጠቃሚ አለመሆኑን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትርዎ ዘርዝሮ ሲያስረዳ፤ የፌደሬሽን ደጋፊ ሆኖ መገመቱ እጅግ ያሳዝናል ሲሉ ወልደጊዮርጊስ የገለጹትን አስተያየት፤ ንጉሠ ነገሥቱ በደህና መንፈስ አልተቀበሉትም። ወዲያውም በሰጡት መልስ፤ ... የፌዴሬሽኑ መፍረስ ጉዳይ የሚታሰበውም የሚዘጋጀውም በኤርትራውያኖቹ መሆን አለበት እያላችሁ፤ አንተና አክሊሉ የተናገራችሁት ከምን የተነሣ እንደሆነ አልተረዳነውም ካሉ በኋላ፤ የኤርትራ ፌዴሬሽን ሕግ ባልተከተለ መንገድ እንዲፈርስ እኛም የማንፈቅድ መሆናችንን ካንተ ከጽሕፈት ሚኒስትራችን የተሻለ የሚያውቅ ማን ነው? በማለት ንጉሠ ነገሥቱ ቅሬታቸውን ገለጡ።

እዚህ ላይ እንደሚታየው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ የተናገሩት፤ የፌዴሬሽኑ መፍረስ ከሚያስከትለው ጣጣ ለመዳን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ያቀረቡት ሐሳብ የሚደገፍ መሆኑን ለማስረዳት ስለሆነ፤ በደህናው ዘመን ቢሆን ኖሮ ይህን የመሰለው ወቀሳ ይሰነዘርባቸዋል ተብሎ የሚጠበቅ አልነበረም። ነገር ግን በንጉሠ ነገሥቱና በጽሕፈት ሚኒስትሩ መካከል የነበረው የጋለ ግንኙነት መቀዝቀዝ ስለጀመረ፤ የጃንሆይ አነጋገር ከልማዱ ውጭ ሆነ። ወልደጊዮርጊስ ይህን ሁሉ ልባቸው የተረዳው ቢሆንም፤ ለተመልካች ምንም ነገር እንደሌለ ለማስመሰል በሥራቸው ላይ የተለመደ ጥረታቸውን አላቋረጡም። ለአሜሪካው ጉዞ ዝግጅት እንዳደረጉት ሁሉ፤ ንጉሠ ነገሥቱ በአውሮፓ አገሮች በተለይም በእንግሊዝና በፈረንሣይ መንግሥታት ዘንድ የሚያደርጉትን የኦፊሲየል ጉብኝት፤ በሳምንት ሦስት ጊዜ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር እየሄዱ ፕሮግራሙን በዝርዝር ማቀናበር ዋና ሥራ አድርገውት ነበር።

የጉብኝቱ ዝግጅት ተጠናቅቆ ጉዞው ከመጀመሩ ከጥቂት ቀናት በፊት፣ ንጉሠ ነገሥቱ ዋና የክብር ተከታዮቻቸውን ሲመርጡ፤

- ልዑል መኰንን መስፍነ ሐረር፣
- ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር፣
- አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፣
- ደጃዝማች መስፍን ስለሺ የከፋ ጠቅላይ ገዢ፣
- አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ የግርማዊነታቸው ልዩ ጸሐፊ፣
- ኰሎኔል መኰንን ደነቀ የግርማዊነታቸው ዋና የእልፍኝ አስከልካይ፣
- ልጅ እንዳልካቸው መኰንን የፕሮቶኮል ሹም፣

መሆናቸውን ባለጉዳዮቹን ሰብስበው አስታወቁ። በዚህ ጊዜ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ያለ ልማዳቸው በጠንከረ አነጋገር፣ በእኔ ቦታ ሌላ ሰው ቢመደብ ይሻላል አሉ። ጃንሆይም በቁጣ ቃል "የለም አንተ ትሄዳለህ፤ ሌላ ሰው አይመደብም" ብለው ወሰኑ። እርግጥ ጸሐፊ ትዕዛዝ ለአሜሪካውም ጉዞ እኔ ብቀር ይሻላል ብለው አመልክተዋል። ያን ጊዜ የሰጡት ምክንያት፣ እናቴ በዕድሜም በጤናም ስለተዳከሙች፣ ቀባሪ እንዳታጣ ብዬ ነው የሚል ነበር። ለዚህ ለአውሮፓው ጉዞ ግን ምንም ዓይነት ምክንያት አላቀረቡም። በአሜሪካው ጉዞ ጊዜ ለመሄድ ያልፈለጉት፣ በፕሮቶኮሉ ዝግጅት ቅር ስለተሰኙ ነው ተብሎ የተሰጠው ትርጉም ትክክል ከሆነ፣ በአሁኑ በአውሮፓው ጉብኝት የጦር ሚኒስትሩ የገቤኔራል ዓቢይ አበበ አለመኖር፣ የወልደጊዮርጊስን የክብር ቦታ ከልዑል መኰንን እንዲቀጥል ስለአደረገው፣ ከአሜሪካው እጅግ የተሻለ መሆኑ ግልጽ ነው። ስለዚህ ወልደጊዮርጊስ በተለይ ከአውሮፓው ጉዞ ልቅር ብለው ያመለከቱት፣ እንደ አሜሪካው በፕሮቶኮል ጉዳይ ሳይሆን፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ያላቸው ግንኙነት የሻከረ መሆኑ ስለተሰማቸው ነው ቢባል፣ ትክክል ይሆናል።

## የጠቡ አጀማመር ... ከአክሊሉ ጋር

በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና በሀብተወልድ ወንድማማቾች መካከል የነበረው ፍቅር ፈርሶ፣ ጠብ እየከረረ መምጣቱ በይፋ የታወቀው ቀስ በቀስና ደረጃ በደረጃ ሲሆን፣ የመጀመሪያው ግጭት የደረሰው ከአክሊሉ ሀብተወልድ ጋር ነበር። በጥቅምት ወር 1947 ዓ.ም፣ ንጉሠ ነገሥቱ አውሮፓን በሚጐበኙበት ጊዜ፣ በእንግሊዝና በፈረንሣይ አገሮች በጸሐፊ ትዕዛዝና በውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ መካከል ስለደረሰው ግጭት፣ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ ለደራሲው የገለጹለት የሚከተውን ነው።

" ... ለአውሮፓው ጉብኝት የክብር ተከታዮች እንድንሆን የተመደብነው ሰዎች ግቢ ተጠርተን በተነገረን ጊዜ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በእኔ ቦታ ሌላ ሰው ቢደረግበት ይሻላል ብለው ሲያመለክቱና ጃንሆይም አንተ መሄድ አለብህ ብለው በከረረ ቃል መልስ ሲሰጡ ያየሁት ሁኔታ ለመጀመሪያ ጊዜ ስለሆነ፣ ምን ደረሰ ብዬ በጣም ደነገጥኩ። በዚያ የነበሩት ሌሎቹ ደጃዝማች መስፍን ስለሺና፣ አቶ ተፈራወርቅ ምንም ዓይነት ስሜት አልታየባቸውም። ምናልባት ቀደም ሲል የሚያውቁት ነገር ይኖራል ብዬ አሰብኩ። የሆነ ሆኖ፣ ጃንሆይና ጸሐፊ ትዕዛዝ

ለብዙ ዘመናት ቅርበትና ወዳጅነት ስላላቸው፣ ይህ በመካከላቸው የታየው የቅሬታ መንፈስ በቶሎ ተለውጦ እቀድሞ ቦታው የሚመለስ እንጂ፣ የሚቀጥልና ጨርሶ ወደ መለያየት ደረጃ የሚያደርሳቸው አልመሰለኝም ነበር።

እንግሊዝ አገር ደርሰን የዐሥራ ሁለቱ ቀናት ጉብኝት እንደተጀመረ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ በእኔ ላይ ያላቸው አመለካከት የተለወጠ ሆኖ አየሁት። ለመጣላትም ምክንያት እንደሚፈልጉ ተረዳሁ። አንድ ጠዋት ጸሐፊ ትዕዛዝ በማረፊያቸው ሆነው መንገሻ ወልደማርያም በተባለው በጃንሆይ አሽከር በኩል በአስቸኳይ እንድትመጣ የሚል መልዕክት ላኩብኝ። እኔም እንደተለመደው ጥሪያቸውን አክብሬ ወደ ማረፊያቸው በፍጥነት ሄድኩ። ብድግ ብለው የቀዘቀዘ ሰላምታ ከሰጡኝ በኋላ፣ አንዳንድ ጉዳዮች መነጋገር አለብን አሉኝ። እሺ ብዬ ወንበር ያዝኩ።

"የዚህ የእንግሊዝ አገር ጉብኝት ከመፈጸሙ በፊት፣ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ከአንቶኒ ኤደን ጋር ተነጋግረህ የታላቋ ብሪታንያ ባለሥልጣኖች ካለፉት ዐሥራ አራት ዓመታት ጀምሮ በጊዜያዊ የጦር ማሳረፊያ ስም የያዙትን የኦጋዴንን ግዛታችንን በአስቸኳይ ለቅቀው እንዲወጡ አንድ ስምምነት መፈራረም አለብህ" በማለት ከልማዳቸው ውጭ የሆነ የጠነከረ ቃል ተናገሩ። አኳኋናቸው ጠብ ፍለጋ መሆኑ ስለገባኝ፣ ጉዳዩን አለስልሼ ባጭሩ ለማስረዳት ሞከርኩ።

" ... ጸሐፊ ትዕዛዝ እንደሚያውቁት በዚህ በጃንሆይ በአውሮፖ ጉብኝት ላይ፣

1ኛ/ ከእንግሊዞች ጋር ተነጋግረን የኦጋዴን ግዛታችንን ለቅቀው የሚወጡበትን ቀን ለማስወሰን፣

2ኛ/ በባቡሩ ጉዳይ ከፈረንሣይ መንግሥት ጋር ተደራድረን በካፒታሉም ሆነ በአስተዳደሩ የኢትዮጵያ መብት በእኩል ደረጃ ሆኖ ስምምነቱ እንዲፈረም ማድረግ እንዳለብን ገና ከአዲስ አበባ ከመነሣታችን በፊት የተወሰነ ነው።

በአሁኑ ሰዓት ከእንግሊዞች ጋር የጀመርነው ንግግር በጣም ተስፋ የሚሰጥ ቢሆንም፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ እንዳሉት የጃንሆይ ጉብኝት ከመፈጸሙ በፊት ውሉን ለመፈራረም እንችላለን ብዬ ቃል አልገባም። ትዕግሥትና ጊዜ ይጠይቀናል አልኳቸው። ቱግ አሉ። የማልጠብቀው መልስ ሰጡኝ። " ... ትዕግሥትና ጊዜ ይጠይቃል እያልክ የምትሰጠው ምክንያት አልገባኝም። ከዚህ ቀደም በዚሁ በኦጋዴን ጉዳይ ጃንሆይ እኔ ባለሁበት ደጋግመው ነግረውሃል። ከዚያ ወዲህ ምንም አጥጋቢ የሆነ ውጤት አልታየም። ስለዚህ ሥራው ስልችቶህ ወይም አድክሞህ እንደሆነ ገልጠህ ብትናገር ይሻላል ... " አሉኝ። በዚህ ጊዜ እኔም ስሜቴን መቆጣጠር አቃተኝ። " ... እኔ ለአገሬ ጉዳይ ስልቹም ደካማም አይደለሁም። ሥራውንም እኔ አልችለውም ወይም አልቻልኩም ብዬ አልመልስልዎትም። እርስዎ ግን አክሊሉ ሥራውን አልቻለውም ብለው የሚያምኑ ከሆነ፣ ጉዳዩን ለጃንሆይ አቅርበው በቦታዬ ሌላ ሰው ያስደርጉ ... " ብያቸው ወጣሁ።

ወደ ማረፊያዬ ተመልሼ ይህን የደረሰውን ግጭት ሳሰላስል፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ እስከዚህ ድረስ ሊያሳዝኑኝ የፈለጉበት ምክንያታቸው ምን መሆኑን መረዳት አልቻልኩም። አብረን በቅርብ ስንሠራ ዐሥራ ሁለት ዓመት አልፏል። በዚህ ሁሉ



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና ንግሥት ኤልሣቤጥ የወዳጅነት ጭውውት ሲያደርጉ፤

ሰር ዊንስተን ቸርችል ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የተለየ አክብሮት ሲሰጡ፤ (ፎቶ ኢ.ጥ.ም.ተ)

ጊዜ ሲረዱኝና ሲወዱኝ የኖሩ ወዳጄ ናቸው። ታላቅነታቸው፣ አገልግሎታቸውና ኤክስፔሪያንሳቸው ከሁላችን የበለጠና የሚከበር መሆኑ ጥርጥር የለውም። ቢሆንም **ዛሬ እኔም እንደእሳቸው የንጉሠ ነገሥቱ ካቢኔ ሚኒስትር ነኝ። የሥራ ጓደኛቸው መሆኔ ቀርቶ እንደ አንድ የሥራ ባልደረባቸው ቆጥረው እስከዚህ ድረስ መናገር አልነበረባቸውም።** እስከዛሬ እንደማውቃቸው፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ አንድ ሚኒስትር በሥራው መዝለፍ የሚጀምሩት፣ በቅድሚያ ጃንሆይን አዘጋጅተው ለማሻር ወይም ለማባረር ሲፈልጉ ነው። እኔም የዚህ ዓይነቱ ዕጣ የሚደርስብኝ መሆን አለመሆኔን ለማወቅ ለምን ጃንሆይን በማነጋገር መንፈሳቸውን ለመረዳት አልሞክርም? ብዬ ወሰንኩ። ጃንሆይ! አንድ ችግር ስላለኝ ለብቻ ያነጋግሩኝ ብዬ ስጠይቅ ተፈቀደልኝ።

" ... በኦጋዴን ግዛታችን ጉዳይ እስካሁን የተደረገውን ሁሉ ጃንሆይ ያውቁታል። እንግሊዝ አገር ከመጣንም በኋላ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ጋር ተነጋግሬ፣ የእንግሊዝ የጦር ሠራዊት ኦጋዴንን የሚለቅበትንና እኛም የምንረከብበትን ቀን ለመወሰን ኤክስፐርቶቹ በማጥናት ላይ ናቸው። ስለዚሁ ጉዳይ ትናንት ጠዋት ጸሐፊ ትዕዛዝ ጠርተው ጠይቀውኝ፣ አሁን የደረስንበትን ሁኔታ አስረድቻቸው ነበር። እሳቸው ግን ይህ በቂ አይደለም። የጃንሆይ ጉብኝት ከመፈጸሙ በፊት እንግሊዞች ኦጋዴንን የሚለቁበት ቀኑ ተወስኖ ስምምነቱን መፈረም አለብህ። አለበለዚያ ሥራው አቅቶህ ወይም ስልችቶህ እንደሆነ ብታመለክት ይሻላል በሚል ንግግር አሳዝነውኛል። ከሁሉ ይበልጥ በጣም የነካኝ፣ **"ሥራው ስልችቶህ እንደሆነ" የሚለው ቃል ነው። እንዴት በአገሬ ጉዳይ ስለቸህ ወይ? ተብዬ እጠየቃለሁ። በችሎታና በዕውቀት ከእኔ የተሻለ የለም ብዬ አልከራከርም። ነገር ግን ለአገር ጉዳይ በማሰብና በመታገል ከጃንሆይ አገልጋዮች የማንስ ነኝ ብዬ አላምንም። ጃንሆይ አሳድገውና አስተምረው ለዚህ ደረጃ አብቅተውኛል። በውነት በእኔ በኩል በሥራ ያጓደልኩት ነገር እንዳል፣ ጃንሆይ ቢነግሩኝ ደስ ይለኛል ...** " አልኳቸው።

ጃንሆይ ሲያነጋግሩኝ ከወትሮአቸው የተለየ አኳኋን አየሁባቸው። ዓይናቸውን ወደ ግድግዳው ትክ አድርገው፣ **" ... ወልደጊዮርጊስ ባሕሪው ተለውጧል። ልቡም ከእኛ ርቋል። ወዳጁን መኰንን ሀብተወልድንም ጠልቷል። አንተንም ከእሱ ጋር ደርቦሃል። ምን እንደሚፈልግ አልገባንም። እግዚአብሔር እየመራን ሁሉንም ወደፊት እስከምናስተካክለው ድረስ ትዕግሥታችን ሰፊ ነው። አንተም ማንኛውንም በልብህ ያዘው። ለእሱም አክብሮትህን እንጂ ቅሬታህን አታሳየው፡ ስለ ኦጋዴንም ጉዳይ የጀመርከውን ቀጥል። ጉዳያችንም በሰላም መንገድ እንጂ በንትርክ እንዲያልቅ አንፈልግም ...** " ብለው አሰናበቱኝ።

ጃንሆይ የተናገሩት የማልጠብቀው በመሆኑ በጣም ገረመኝ። የጸሐፊ ትዕዛዝና የአቶ መኰንን መጋጨት የእኔም እዚህ ውስጥ መጨመር፣ እጅግ አሳዘነኝ። ጃንሆይ፣ **"ማንኛውንም በልብህ ያዘው"** ብለው ስለአስጠነቀቁኝ፣ አዲስ አበባ ተመልሼ እውነተኛውን ጉዳይ እስከምረዳ ድረስ፣ ከማንም ጋር መነጋገር አያስፈልግም ብዬ ወሰንኩ። እስከዚያም ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር የቀድሞ አክብሮቴን ሳላለውጥ ቀጠልኩ። እሳቸው ግን በእኔ ላይ ቅሬታ ያላቸው መሆኑን ያስሙኝ **ነበር። ሲያነጋግሩኝም እንደቀድሞው በቅርበት መንፈስ ሳይሆን፣ በርቀት "ክቡር አቶ አክሊሉ"** ማለት ጀመሩ። በዚህ አኳኋን የእንግሊዙ ጉብኝት ተፈጽሞ የፈረንሣዩ አገር ከተጀመረ በኋላ፣ ሌላ ያለመግባባት ታሪክ ተጨመረበት።



የፈረንሣይ ሬፑብሊክ ፕሬዚዳንት
ሬኔ ኮቲና የጠቅላይ
ሚኒስትር ማንዴስ ፍራንስ
ባለቤት፤ ንጉሠ ነገሥቱን
ለራት ግብዣ ሲቀበሉ፤



ብዙ ጊዜ የፈረንሣይ ጠቅላይ
ሚኒስትር የነበሩና፤ የኢትዮጵያ
ዋና ወዳጅ የሆኑትን
"ኤድዋርድ ሔሪዮን" ጃንሆይ
በጋለ መንፈስ ሲቀበሉ፤

አንድ ቀን በፓሪስ ማረፊያችን በክሪዮን ሆቴል (Hotel Crillon) ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፣ የኢትዮጵያ አምባሳደር ብላታ ኤፍሬም ተወልደመድህንና እኔ እንዲሁም ሌሎች ስማቸውን የዘነጋሁት ሁለት ሰዎች ባለንበት፣ ያለፈ ታሪክ በማውሳት የፈረንሣይ መንግሥት በፋሽስት ዘመንና ከዚያም በኋላ በኤርትራ ጉዳይ ረዳታችን አልነበረም፣ እያልን መጨዋወት ጀመርን። በዚህ ጊዜ ጸሐፊ ትዕዛዝ በድንገት ተነሥተው፣ " ... ኤርትራን እኮ ያስመለስኩ እኔ ነኝ፤ ሌላው ሁሉ ከንቱ ነው ... " የሚል መግለጫ ሰጡ። ለጊዜው ሁላችንም ደንግጠን ፀጥ አልን። ያስደነገጠን ከንግግሩ ቃል ይልቅ ሁኔታቸውና የሰውነታቸው መለዋወጥ ነው። ብላታ ኤፍሬምና ሌሎቹም ክፍሉን ትተው ወጡ። እሳቸውና እኔ ብቻችንን ቀረን። ከጥቂት ደቂቃ በኋላ፣ " ... ጸሐፊ ትዕዛዝ! አሁን የተናገሩት አልገባኝም። ኤርትራን ያስመለስኩት እኔ ነኝ፤ ሌላው ሁሉ ከንቱ ነው ሲሉ ምን ማለትዎ ነው? ... " ብዬ ጠየቅኋቸው።

" ... ያልኩት ትክክለኛውን ነው። አንተ በኤርትራ ጉዳይ ከፍተኛ ዝና ያገኘኸው በእኔ ነው። እኔ ባልኖር ይህን ዕድል አታገኘውም ነበር ... " አሉኝ። " ... እኔ እኮ ለሥራዬ መቃናት አልረዱኝም ብዬ አላውቅም። በእርግጥም የርስዎን ድጋፍና እርዳታ ምንጊዜም የምዘነጋው አይደለም። የኤርትራ ጉዳይ በታላላቅ መንግሥታት ሸንጐና በተባበሩት መንግሥታት ጉባኤ ላይ ለፍርድ ቀርቦ ሲታይ፣ ከጠላት አገሮች ጋር ተጋፍጬ የተሟገትኩትና በመጨረሻም ድልን ያስገኘሁ መሆኔን ከርስዎ የበለጠ ማንም ሊመሰክር አይችልም። ለዚህም እርስዎ በብዕርዎ ጽፈው የገለጿቸው አስተያየቶች ሰነድ ሆነው መቅረብ ይችላሉ። ይህንን ስል በኤርትራ ጉዳይ የእርስዎም ድካም ምን ያህል ከፍተኛ እንሆነ በሚገባ እመሰክራለሁ። በአገር ውስጥ የኤርትራውያኖች የአንድነት ትግል እንዲበረታና የዓለምን አስተያየት እንዲማርክ ያስተባበሩት ትልቁ ቁልፍ እርስዎ ነዎት። በውጭውም አገር በእኔ የሚመራው የኢትዮጵያ መልዕክተኞች ቡድን በዓለም ሸንጐ ላይ ፍርድ ለማግኘት እንዲሳካለት፣ አስፈላጊውን ድጋፍ ያቀረቡለት እርስዎ ነዎት። ነገር ግን ቀደም ሲል እንደተናገሩት፣ ኤርትራን ያስመለሱ እርስዎ ብቻ ሆነው ሌላው ሁሉ ከንቱ ነው ማለት አይችሉም። ይህም ዓይነቱ አነጋገር ከርስዎ የሚጠበቅ ባለመሆኑ እጅግ ማዘኔን፣ ከዚህም አልፎ መቀየሜን እንዲያውቁት እፈልጋለሁ ... " አልኳቸው።

የተናገርኩትን በእርጋታና በፀጥታ ካዳመጡ በኋላ የሰጡኝ መልስ፣ በመካከላችን የነበረው ወዳጅነት እቀድሞ ቦታው እንዲመለስ የሚረዳ አልነበረም።

" ... የተናገርከው ከሞላ ጐደል ልክ ነው። ሞያህ ጥብቅና ስለሆነ፣ መናገር ታውቅበታለህ። ሆኖም አንተ ያልተናገርካቸው እኔ ለአንተ ያደረግኋቸው ብዙ ነገሮች ነበሩ። የቀረው ቢቀር እስከዛሬ ድረስ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሆነህ ለመቆየት የቻልከው፣ በእኔ ኃይልና ድጋፍ መሆኑን ልታውቀው ይገባ ነበር። አንተን ከውጭ ጉዳይ ለማስነሣት እንግሊዞችና አሜሪካኖች የሞከሩትን ታግዬ ያስቀረሁ እኔ መሆኔን ልብህ ያውቀዋል። ግን መናገር አትፈልግም ... " አሉኝ። ወዲያው ጸሐፊ ትዕዛዝ! እዚህ ላይ ይፍቀዱልኝና እኔም የልቤን ልናገር አልኳቸው።

" ... እኔ በሥራዬ ምን ያህል ይረዱኝ፣ ምን ያህል ይታገሉልኝ እንደነበረ የማውቀውን ሁሉ በሚገባ ገልጬልዎታለሁ። ከዚህ የበለጠ ሐሳቤን የምገልጽባቸው ቃላቶች የሉኝም። እርግጥ! ያልጠቀስኩት ወይም በግልጽ ያልተናገርኩት፣ እኔ

ከውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር እንድሻር ወይም እንድዛወር ከአገር ውስጥ መኳንንትና ከውጭ አገር መንግሥታት በተሞከረ ጊዜ፤ እርስዎ የተጫወቱትን ሚና (ሮል) ነው። እንደማውቀው በእኔ ቦታ መሾም ይገባቸዋል የተባሉት ዕጩዎች፤ ይልማ ዴሬሣ ወይም መኰንን ደስታ ነበሩ። ሁለቱም የተማሩና አገራቸውን የሚወዱ ሰዎች ናቸው። ይሁን እንጂ እነዚህ ሁለቱም ሰዎች ለርስዎ አመራር ምቹ ስላልሆኑ፤ አክሊሉ ቢቆይ ይሻላል ብለው እኔን መምረጥዎን የሚክድ የለም። እንደሚያውቁት በፖለቲካ ሥራ ውስጥ ሰው ሁሉ የሚደጋገፈው ጥቅሙን በማሰብ ነው እንጂ፤ እንደ መንፈሳዊ ሥራ ለጽድቀት ይቆጠርልኛል ብሎ አይደለም። እርስዎ እኔን አክሊሉን ውጭ ጉዳይ ማቆየት አለብኝ ብለው እንደታገሉት ሁሉ፤ እኔም ወልደጊዮርጊስ በሥልጣናቸው ይቆዩልኝ ብዬ መመኘቴ አልቀረም። ሆኖም ቤተእግዚአብሔር ሄጄ ጸልዩልዎት ነበር ብልዎት አያምኑኝም። ከልቤ ተመኝቼ ነበር ብልዎት ግን ሊቀበሉኝ ይገባል። (እዚህ ላይ በጣም ሳቁ)

እንግዲህ! እርስዎ ለእኔ ያደረጉትን ሁሉ ሲናገሩ እኔ ደግሞ የርስዎን ወዳጅነት ተመርኩዤ ምን ያህል እርዳታ አቀርብልዎት እንደነበረ፤ እርስዎ አንድም ቃል አልተናገሩም። እኔም አልናገርም። አሁን ይህን ሁሉ ያለፈ ነገር ትተን፤ ዛሬ በርስዎና በእኔ መካከል ምን ደርሶ ነው ይህን ያህል መወቃቀስ ላይ የጣለን? ብለን ብንነጋገር ይሻላል። ነገሩ የተጀመረው ከእርስዎ ስለሆነ እኔ ምን እንደበደልኩ ቢነግሩኝ በጣም እደሰት ነበር ... " አልኳቸው።

ጥሩ አጋጣሚ ነው፤ እኔም ሁሉንም ሳልደብቅ እነግርሃለሁ ብለው ጀመሩ።

" ... አንተ ለእኔ ያለህን ወዳጅነት አልለወጥኩም የምትለውን ለማመን ያቅተኛል። ከወንድምህ ከአቶ መኰንን ጋር ሆናችሁ፤ ዘመዳችሁን ሣህሉ ድፋዬን ጨምራችሁ፤ እኔን ከጃንሆይ ጋር ለማጣላትና ለማለያየት የምትሠሩትን ሁሉ ደርሼበታለሁ። "ሰውን ውደደው እንጂ አትመነው" ይላል እውነተኛው መጽሐፍ። እኔ ወልደጊዮርጊስ ከእናንተ ከሀብተወልድ ወንድማማቾች ጋር ለብዙ ዘመናት አብሬአችሁ ስሠራ፤ ከመውደዴ አልፌ እምነቴን መጣል አልነበረብኝም። ከእናንተ ጋር ሆኜ የኛ የድሆች ተቃዋሚዎቻችን ከሆኑት ከመሳፍንትና ከመኳንንት ጋር ስዋጋና ሳሸንፍ ከኖርኩ በኋላ፤ ዛሬ ደግሞ እናንተ ከእኔ ተለይታችሁ ከእነዚሁ የጋራ ጠላቶቻችን ከሆኑት ጋር በመሰለፍ፤ እኔን ለማጥቃት ትጥራላችሁ ብዬ አላስብም ነበር። የዕውቀቴ ማጠር የበደለኝ፤ ይህ ይደርሳል ብዬ አርቄ አለመመልከቴ ነው። ይሁን እንጂ፤ ይህ በእኔ ላይ የምትጐነጉኑት ተንኮል፤ ለከፍተኛ ትዝብትና ውርደት ያበቃችሁ ይሆናል እንጂ፤ የምትፈልጉትን አያስገኝላችሁም። ታያላችሁ አይቀናችሁም ... " ብለው የፈገግታ ምልክት አሳዩኝ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን እኔ እንደማውቃቸው ይህን የመሳሰለ እስከ አጥንት የሚዘልቅ ንግግር ሲወረውሩ የሚያሳዩት ፈገግታ በውስጣቸው ምን ያህል እንደተበሳጩና ምን ያህል እንዳዘኑ የሚያመለክት ነው። በእኛ በሀብተወልድ ወንድማማቾች ላይ የተናገሩት እኔንም በጣም የነካኝና ያሳዘነኝ ቢሆንም፤ በምሰጣቸው መልስ እሳቸውን የበለጠ ብስጭት ላይ እንዳልጥላቸው የምናገረውን ሁሉ መመዘን ነበረብኝ። ጸሐፊ ትዕዛዝ! አሁን የምናገረው ሁሉ በእውነት ላይ የተመሠረተ መሆኑን እንዲረዱት፤ የእግዚአብሔርን ስም እጠራልዎታለሁ ብዬ ሐሳቤን መግለጽ ጀመርኩ።

" ... እኛ ሀብተወልድ ወንድማማቾች እየተባልን የምንጠራ ሰዎች፤ በጃንሆይ መንግሥት ውስጥ የካቢኔ አባልነት ደረጃ ከተቀበልንበት ጊዜ ጀምሮ፤ ወዳጆቻችንን ለመጥቀም፤ ተቃዋሚዎቻችንን ለማጥቃት በሕብረት ቆመን የታየንበት ጊዜ የለም።

በሕይወታችን ላይ የሚደርሰውን ክፉውንም ሆነ ደስታውን የምንቀበለው በየግላችን ስሜትና አመለካከት ነው። ከዚህም በላይ ሦስታችንም ምንም እንኳ ከአንድ አባትና ከአንድ እናት የተወለድን ብንሆንም፤ በአስተሳሰባችን ሆነ በጠባያችን፣ በአኗኗራችን ሆነ በሕይወት ጣዕማችን፣ በችሎታችን ሆነ በሥራ ዝንባሌያችን፤ እጅግ የተለያየን ወንድማማቾች መሆናችን ከርስዎ የበለጠ የሚያውቀው ይኖራል አልልም። እስከ ዛሬም ድረስ ሦስታችንም የርስዎ ወዳጆችና የርስዎ ተባባሪዎች ሆነን ኖረናል። አሁን ግን እርስዎ እንደተናገሩት፤ ወዳጅነታችንን ለውጠን እርስዎን ከጃንሆይ ለማጣላትና ለማለያየት የምንጥር መሆናችን ተደርሶበታል ብለውናል። በዚህ ጉዳይ እኔ የማቀርብልዎ ጥያቄዎች አሉኝ። ፈቃድዎ ሆኖ ቢመልሱልኝ በጣም ደስ ይለኛል።

አንደኛ/ አቶ መኰንን እና እኔ እርስዎን ከጃንሆይ ጋር ለማጣላት የምንችለው፤ በርስዎ ላይ ምን ወንጀል አግኝተን ነው? ደግሞስ ምን ጥቅም ለማግኘት ነው?

ሁለተኛ/ እርስዎ ጥሩ አድርገው የሚያውቋቸው ጃንሆይ፤ እርስዎን ከሥልጣን ለማንሣት መመካከር የሚያስፈልጋቸው ከሆነ፤ ከእኛ በተለይም ከእኔ የተሻሉ ሕዝብ የሚያከብራቸውና የሚያዳምጣቸው ታላላቅ ሰዎች የሏቸውም ወይ?

ሦስተኛ/ እንደ እኔ የመሰለው፤ በውጭው ዓለምና በውጭ ጉዳይ ሥራ ብቻ ተወስኖ የሚኖር ሰው፤ እርስዎን እጅግ በከበደው የአገር አስተዳደር ሥልጣን ላይ ለመወንጀልም ሆነ ለመደገፍ፤ በየትኛው ዕውቀቱና በየትኛው ልምዱ ለንጉሠ ነገሥቱ አስተያየት አቅራቢ መሆን ይችላል ብለው ያምናሉ?

ስለዚህ በዛሬው ቀን በበኩሌ አጠንክሬ የምሰጠው አጠቃላይ መልስ፤ እኔ እርስዎን ከጃንሆይ ጋር በማጣላት ምንም ዓይነት ፍላጐት ያላደረብኝና፤ ብፈልግም እንኳ ምንም ዓይነት አቅምና ችሎታ የሌለኝ መሆኑን እንዲገነዘቡልኝ ብቻ ነው። ስለወንድሜ ስለ አቶ መኰንን ለተናገሩት እኔ በቀጥታ መልስ መስጠት አልፈልግም። በርስዎና በእሱ መካከል ያለውን ፍቅርና የጠበቀ የወዳጅነት ግንኙነት ማንም ሊበጥሰው አይችልም። ስለዚህ፤ በእርስዎም ሆነ በእሱ በኩል አንዳንድ ችግር ቢፈጠር፤ ሁለታችሁ በቀጥታ ተነጋግራችሁ መድኃኒቱን ማግኘት አለባችሁ። ወዳጅነታችሁን ለመጠበቅም ሆነ ለማፍረስ፤ ባለቤቶቹ እናንተ ብቻ ናችሁ ... " ብዬ የማስበውን ሁሉ ገለጽኩላቸው። እሳቸውም መልስ ለመስጠት ሲጀምሩ፤ በድንገት ኰሎኔል መኰንን ደነቀ* በሩን ስማህ! አቶ አክሊሉ ብለው ከፍቶ ገባና እኔን ጃንሆይ በአስቸኳይ ይፈልጉሃል ብሎ ጠራኝ። ጸሐፊ ትዕዛዝም እንግዲያው የጀመርነውን ስትመለስ እንቀጥልበታለን ብለውኝ ወደተጠራሁበት ሄድኩ።

ጃንሆይ የፈለጉኝ ትናንት ማታ በኬዶርሰይ (Quai D'orsay)* በተደረገው የራት ግብዣ ላይ፤ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትርና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሙሴ ማንዴስ ፍራንስ (Mendès France) ሲያነጋግራቸው፤ በኢትዮጵያና በፈረንሣይ የምድር ባቡር ጉዳይ፤ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትርዎ ጋር ለመግባባት ሳንችል ቀርተናል የሚል

---

* የንጉሠ ነገሥቱ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ

* የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ቤልግሬድ ሄደው፤ ከፕሬዚዳንት ጆዜፍ ብሮዝ ቲቶ
ከፍ ያለ የወዳጅነት አቀባበል ሲደረግላቸው፤

ወቀሳ ስለሰነዘረላቸው፤ ችግሩ ምን እንደሆነ እንዳስረዳቸው ነበር። ለወትሮው ጃንሆይ አንድ ነገር ሲሰሙ ወዲያውኑ ጠርተው አስረዳኝ ይሉኝ ነበር እንጂ፤ እንደዚህ አሳድረውና አውለው ከጠየቁኝ፤ አንድ ደስ ያላላቸው ነገር ይኖራል ብዬ ጠረጠርኩ።

" ... የዚህን የባቡር ጉዳይ ጃንሆይ ከአዲስ አበባ ከመነሣትዎ በፊት፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ባሉበት ያቀረብኩትን ጥናት ጃንሆይ አጽድቀውታል። ይኸውም ኢትዮጵያና ፈረንሣይ በእኩል ደረጃ ካፒታሉን እንዲካፈሉና በእኩል ደረጃ አስተዳደሩን እንዲመሩ ነው። ፈረንሣዮች የሚፈልጉት፤ እስካሁን እንደነበረው የኩባንያው ዋናዎቹ ባለቤቶች እነሱ ሆነው፤ በአስተዳደሩ ውስጥ ለእኛ አንድ ወይም ቢበዛ ሁለት የቦርድ አባልነት ቦታ ለመስጠት ነው። ይህንን የፈረንሣይ ሐሳብ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር በሰፊው ተነጋግረን ቀደም ሲል ጃንሆይ በወሰኑት መሠረት አንቀበልም ብሎ መከራከሩ የሚጠቅም ሆኖ አግኝተነዋል። ሙሴ ማንዴስ ፍራንስ በውጭ ጉዳይ ሚኒስትርነቱ እኔን እቢሮው ተቀብሎ ባነጋገረኝ ጊዜ፤ ይህንኑ የኢትዮጵያን ሐሳብ ደህና አድርጌ አስረድቼው ነበር። ትናንት ማታ በጠቅላይ ሚኒስትርነቱ ለጃንሆይ ባደረገው የራት ግብዣ ላይ፤ ይህንን የባቡሩን ጉዳይ አንሥቶ ከእኔ ጋር አለመግባባታችንን የገለጸልዎ፤ ያለ ጥርጥር ከእኛ በኩል የቀረበውን ሐሳብ የማይቀበል መሆኑን ለማስረዳት ነው። እኛ ግን በጀመርነው መቀጠልና ጠንክረን መከራከር የሚያስፈልግ ይመስለኛል ... " አልኳቸው። ጉዳዩን በማስረዳበት ጊዜ ጃንሆይ የሚያዳምጡኝ ፊታቸውን አጥቁረው ስለሆነ፤ የማገኘው መልስ የሠራሁትን የሚነቅፍ እንደሚሆን ተሰምቶኝ ነበር።

" ... እኛ ሳናውቅ ወልደጊዮርጊስና አንተ እየተመካከራችሁ የምትወስኑ ከሆነ፤ የፈረንሣይ መሪ የሆነው ጠቅላይ ሚኒስትር ሲጠይቀን ምንድን ነው የምንመልስለት? ይህን የመሰለውን አሠራር ሁለተኛ እንድትደግመው አንፈቅድልህም። የውጭ ጉዳይ ሚኒስትራችን እስከሆንክ ድረስ፤ ትዕዛዝ የመትቀበለው ከእኛ፤ ሐሳብም የምታቀርበው ለእኛ መሆን አለበት እንጂ፤ እዚያና እዚህ ማለት አያስፈልግም። ስለ ባቡሩ የወደፊት አስተዳደር ጉዳይ፤ አሁን የተናገርከውና ከወልደጊዮርጊስም ጋር ተመካክሬያለሁ የምትለው፤ ልክ አይደለም አይባልም። ቢሆንም ሁለታችሁም የረሳችሁት አንድ ትልቅ ነገር አለ። እኛ የፈረንሣይ መንግሥት የክብር እንግዳ ሆነን በኦፊሲየል በመጣንበት ጊዜ፤ ይህንን ከብዙ ጊዜ ጀምሮ ሲያጨቃጭቅ የቆየ ጉዳይ ማንሣትና መሟገት የተገባ አለመሆኑን ማሰብ ነበረባችሁ። ዞሮ ዞሮ ይህ ጉዳይ ውሳኔ ማግኘት ያለበት፤ በወዳጅነትና በመግባባት እንጂ፤ በመጣላት አይሆንም። ለዚህም ከሁለታችንም ከኢትዮጵያም ከፈረንሣይም ወገን ዐዋቂዎች ተመርጠው የቀረቡትን ሐሳቦች እንዲያጠኑትና አንድ አስታራቂ መላ እንዲፈጥሩለት ማድረግ ነው እንጂ፤ አንተ እንደምተለው በእኛ ሐሳብ ፈረንሣዮች መስማማት አለባቸው ብሎ በደረቁ መፎከር የጨዋ ሥራ አይሆንም። ስለዚህ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር ይህን ጉዳይ እንደገና ካነሣብን፤ በዐዋቂዎች ተጠንቶ እንዲቀርብልን ማድረግ ነው ብለን ምላሹን እንሰጠዋለን። አንተም ለእኩዮችህ ባለሥልጣኖች ይህንኑ ንገራቸው ... " ብለው አሰናበቱኝ።

በምድር ባቡሩ ጉዳይ ጃንሆይ የተናገሩት እውነት ነው። የኦፊሲየል ጉብኝት በሚያደርጉበት ሰሞን፤ ከጋባዡ መንግሥት ጋር የሚያቃቅር ነገር እንዳይፈጠር መጠንቀቁ አስፈላጊ ነው። እኔም ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር ተመካክሬ ያቀረብኩት ሐሳብ፤ የእኛን መብት ለፈረንሣዮች አጠንክረን እናስረዳቸው ለማለት ነው እንጂ፤

ወደ ጠብ ለመሄድ አልነበረም። አሁንም ጃንሆይ እንዳሉት ጉዳዩ በኤክስፐርቶች ተጠንቶ እንዲቀርብ ስምምነት ማድረጉ፤ ለጊዜው የተደነቀረውን ጭቅጭቅ አቁሞ ለሌላ ጊዜ ያስተላልፍልናል ለማለት ነው እንጂ፤ መፍትሔ ሆኖ አይደለም። መቸም ከፈረንሣዮች ጋር ያለ ንትርክ በሰላም ስምምነት ይገኛል ብሎ ማሰብ ከንቱ ሕልም ነው።

በዚህ ዕለት ጃንሆይ ከተናገሩት በጣም ያስገረመኝ፤ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር መመካከሬንና እሳቸውም የተስማሙበት መሆኑን ስገልጽላቸው የሰጡኝ መልስ ነው። **"ትዕዛዝ የምትቀበለው ከእኛ ነው። ሐሳብ የምታቀርበውም ለእኛ ነው" የሚለውን ቃል እስከ ዛሬ ስምቼው አላውቅም። ከዚህ ቀደም ብቻዬን አግኝቻቸው አንዳንድ ሐሳብ ሳቀርብላቸው በሚሰጡኝ መልስ፤ ወልደጊዮርጊስ አውቆታል? ተመካክራችኋል? የሚል ጥያቄ ይሰነዝሩ ነበር። ዛሬ ግን ይኸ ሁሉ ተለውጦ እኛ ሳናውቀው የእናንተ መመካከር ብቻ ፍሬ የለውም የሚል ሆነ። እርግጥ ከጥቂት ቀናት በፊት እንግሊዝ አገር የነገሩኝን አስታውሳለሁ። በዚያን ጊዜ የመከሩኝ ወልደጊዮርጊስን ታገሠው። አንተ አትለወጥበት የሚል ስለሆነ፤ እስከዚህ ድረስ የጸሐፊ ትዕዛዝን ሥልጣን በማዳከም፤ እኔ በቀጥታ ከጃንሆይ ጋር ብቻ እንድሠራ የፈለጉ መሆናቸው አልገባኝም ነበር።**

ከጃንሆይ ጋር በረዥሙ ተነጋግሬ ወደ ማረፊያዬ ስመለስ፤ የምሽቱ የራት ፕሮግራም ስለደረሰ፤ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር ጀምረነው የነበረውን መቀጠል አልተቻለም። በእራቱ ግብዣ ላይ ጸሐፊ ትዕዛዝን ሳገኛቸው፤ ከጃንሆይ ጋር ምን አቆየህ? ብለው አልጠየቁኝም። እኔም አላነሣሁባቸውም። ሆኖም አጅሬ አንድ ነገር ሳይጠረጥሩ እንዳልቀሩ ተሰምቶኛል። የዕለቱ ፕሮግራም ተፈጽሞ እኩለ ሌሊት ገደማ ወደ ሆቴል ስገባ፤ ኮሪደሩ ላይ ኮሎኔል መኰንን ደነቀን አገኘሁትና ዲጀስቲፍ* ልጋብዝህ አልኩት። ሳያመነታ እሺ ብሎኝ መጣ። መኰንን ደነቀ የጸሐፊ ትዕዛዝ የቅርብ ወዳጅ ነው። እኔንም ወንድሜ ወዳጄ ይለኛል። ሆኖም ላይ ላዩን የጋለ ሰላምታ ከመለዋወጥ በስተቀር በመንግሥት ሆነ በግል ጉዳይ ተወያይተን አናውቅም። ሐቀኝነቱም እስከምን ድረስ እንደሆነ መገመት አልችልም። ዛሬ ግን ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ አስተያየቱን ልጠይቀው ብዬ ወሰንኩ።

"ስማ! ወዳጄ መኰንን፤ በዚህ በአውሮፓው ጉዞአችን ላይ ከእንግሊዝ አገር ጀምሮ ፈረንሣይም አገር ከመጣን በኋላ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በእኔ ላይ አኳኋናቸው ተለውጧል። አንዳንድ የሚወረውሩትም ቃል የጠብ መጫሪያ መስሎ ታይቶኛል። እኔ በበኩሌ ብቻዬን ባስብና ባሰላስል ምክንያቱን ፈልጌ ማግኘት አልቻልኩም። ስለዚህ ያንተን አስተያየት ማወቅ ይጠቅመኛል ብዬ ወሰንኩ ... " አልኩት። መኰንን ደነቀ ለመልሱ አልተጨነቀም።

" ... ጸሐፊ ትዕዛዝን በትዕግሥት ያዛቸው። በአሁኑ ሰዓት ከፍ ያለ ብስጭት ላይ ናቸው። ጃንሆይ ፊታቸውን ዘወር አድርገውባቸዋል። ለዚህም ምክንያቱ ዋናው አቶ መኰንን ሀብተወልድ ሲሆኑ፤ አንተም ተባብረሃል የሚል ወሬ ሰምተዋል። በዚህ ጉዳይ አንተ እንደሌለህበት እኛ ደህና አድርገን እናውቃለን። **መቸም የጸሐፊ ትዕዛዝ ትልቁ ችግራቸው አንድ ነገር ሲሰሙ ከማጣራት በፊት ያንኑ ነክሰው እርምጃ ለመውሰድ መፍጠናቸው ነው። አንተን በዚህ በገራችን የተንኮል ጥንስስ ውስጥ ማንም አይጠረጥርህም። እኛ የቅርብ ወዳጆቻቸው**

---

* ኮኛክ ወይም ፊርኔት

እናስረዳቸዋልን። ይልቅስ አዲስ አበባ ስንመለስ አንተ አቶ መኰንን ሀብተወልድን እንድትመክራቸው የወንድምነት ሐሳቤን አቀርብልሃለሁ። አቶ መኰንን ጸሐፊ ትዕዛዝን ከጃንሆይ ለማለያየት ኃጢአት ፍለጋ በያለበት ሲቆፍሩ ይውላሉ እየተባለ ይወራባቸዋል። ጸሐፊ ትዕዛዝም ይህን ሰምተው እጅግ አዝነውባቸዋል። በአሁኑ ሰዓት የእነዚህ የሁለቱ የጃንሆይ ታማኞች መጣላት ለአገርም ለመንግሥትም አይበጅም። ስለዚህ ሁላችንም በየበኩላችን በእነዚህ በሁለቱ ታላላቅ ሰዎች መካከል ያለው ፍቅርና መተባበር እንደቀድሞው እንዲቀጥል ብርቱ ጥረት ማድረግ አለብን ... " አለኝ። መኰንን ደነቀ የተናገረውን ካዳመጥኩ በኋላ አንድ ጥያቄ አቀረብኩለት። "ጃንሆይ በጣም ከሚተማመኑባቸውና ሙሉ ሥልጣን ካሸከሟቸው ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር ለምን ይጣላሉ? በዚህስ መካከል አቶ መኰንን እንዴት ሊገባበት ቻለ?" ብዬ ጠየቅኩት። የጃንሆይ የእልፍኝ አስከልካይ መልስ እጅግ አስገረመኝ።

"አንተ ጃንሆይን አታውቃቸውም።"

- ወረተኛ በመሆናቸው፤ ከአንድ ባለሟል ጋር ጸንተው እስከ መጨረሻው አይኖሩም።
- ሸረኛ በመሆናቸው የቅርብ አገልጋዮቻቸው ሲስማሙና ሲተባበሩ አይወዱም።
- በአሁኑ ሰዓት ጃንሆይ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር ያላቸው ግንኙነት የሻከረ መሆኑ ለማናችንም ምሥጢር አይደለም። አንተ እንዴት እንዳልታየህ አልገባኝም። ቀደም ብዬ እንደጠቀስኩልህ፤ እዚህ ላይ አቶ መኰንን ከጃንሆይ ጀርባ ሆነው ጠቡን ለማቀጣጠል በማረገብ ላይ ናቸው ብለው ጸሐፊ ትዕዛዝ አምነውበታል። በቂ መረጃዎችም አግኝቻለሁ ይላሉ።
- እኔ እንደማውቀው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝን ከጃንሆይ ለማለያየት ይጥራሉ የሚባሉት አቶ መኰንን ብቻ አይደሉም። ንጉሣዊ ቤተሰቦች በራስ ካሣ መሪነት በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ ተነሥተዋል። ከሚኒስትሮቹም ራስ አበበ እና ጠቅላይ ሚኒስትሩ ቢትወደድ መኰንን አንድነት ሆነዋል። ይሁን እንጂ በእኔ አስተያየት እነዚህ ሁሉ የሚያደርጉት ጥረት፤ የወልደጊዮርጊስን ሥልጣን ለመናድ ያበቃቸዋል ብዬ አላምንም። እንግዲህ በወዳጅነቴ የማውቀውን አልደበቅኩህም። ከዚህ በተረፈ ያለውን አንተ ተከታትለህ ድረስበት" ብሎኝ ከኛኩን ተጉነጨ።

ከዚህ በኋላ ሌላ ጥያቄ ማቅረብ ወይም የግል አስተያየት መስጠት ጠቃሚ አልመሰለኝም። ኰሎኔል መኰንን ስለገለጸልኝ አስተያየት ሁሉ አመሰግናለሁ ብየው በዚሁ ተለያየን።

መኰንን ደነቀን ከሸኘሁ በኋላ፤ ሳልተኛ ለብዙ ሰዓት ብዙ ነገሮችን ሳወጣና ሳወርድ ቆየሁ። እንቅልፍ የሞከረኝ ወደ ንጋቱ አካባቢ ነበር። ከሁሉ ይበልጥ በጣም የገረመኝ፤ የጃንሆይ የእልፍኝ አሽከር ከእኛ የካቢኔ ሚኒስትሮች ከምንባለው ሰዎች የበለጠ ብዙ ነገሮችን የሚያውቅ መሆኑ ነው። በእኛ ትውልድ የተማሪ ቤት ዘመን፤ በግዴታ የምንማረው የፈረንሣይን ነገሥታት ታሪክ ስለሆነ፤ በዐሥራ ስምንተኛው ክፍለ ዘመን በፀሐዩ ንጉሥ ጊዜ (Au Temps Du Rol Soleil) የሚካሄደው

የቤተመንግሥቱ አሠራር ትዝ አለኝ። ፀሐዩ ንጉሥ፤ ከመሳፍንቶቻቸውና ከታማኝ አገልጋዮቻቸው መካከል፤ የሚሾሙትን ሆነ የሚሽሩትን፤ ወህኒ ቤት የሚልኩትን ሆነ ወደ ግዞት የሚያባርሩትን፤ በቅድሚያ የሚሰሙትና የሚያውቁት የእልፍኝ አሽሮቹ ስለሆኑ፤ ለእነሱ ብዙ ሰው ይሰግድላቸው እንደነበረ የዘመኑ ታሪክ ያስረዳናል። በአገራችንም በዚህ በሐያኛው ክፍለ ዘመን አጋማሽ ላይ፤ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አገልጋይዎች መካከል፤ ሹመት የሚታሰብላቸውንና ሽረት የሚዘጋጅላቸውን ከአዋጅ በፊት በቅድሚያ የሚያውቁት የእልፍኝ አሽከሮቹ መሆናቸውን እኛም ደርሰን የምናየው ሆኗል። ለምሳሌም፤ የዘመናችን ትልቁ ባለሥልጣን ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ በእኔ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ላይ መንፈሳቸው ለምን እንደተለወጠ ለማወቅ የሞከርኩት፤ ከጃንሆይ የእልፍኝ አሽከር እንጂ፤ ከጓደኞቼ ከካቢኔ ሚኒስትሮች ወይም ከታላላቆቹ ሰዎች አይደለም። ስለዚህ እኔም ሳይታወቀኝ፤ በፀሐዩ ንጉሥ ዘመን የነበረው አሠራር በአገራችንም መኖር አለበት ብዬ እምነት አድሮብኛል ማለት ነው።

በአገራችን የአንድ የእልፍኝ አስከልካይ ሥራ፤ የቤተመንግሥቱን ሥርዓት ማስከበር፤ መሳፍንቱንና መኳንንቱን እንደየማዕረጋቸው ማስገባትና ማስወጣት፤ በግብዣም ላይ ተገቢ የሆነውን ወንበራቸውን መስጠትና ማስተናበር ነው እንጂ፤ ከዚህ ሁሉ አልፎ በትልልቁ የፖለቲካ ጉዳይ ውስጥ ገብቶ መካሪና አስተያየት ሰጭ የሚሆን አይመስለኝም ነበር። እኔ መኰንን ደነቀን ሳነጋግር፤ ከእሱ የምፈልገው ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በእኔ ላይ ቅሬታ የሚያሳዩት ለምን ምንደሆነ እንዲነግረኝ ነው እንጂ፤ የንጉሠ ነገሥቱን የሥራ ጠባይ፤ በታማኞቻቸው መካከል ያለውን የፖለቲካ ትርምስና አለመግባባት፤ የታላላቆቹ ባለሥልጣኖች መጣላት ደግሞ፤ ለአገራችን የሚበጅ መሆን አለመሆኑን እሱ እንደ መምህር ሆኖ እንደሚያስረዳኝ፤ እኔም እንደ ተማሪ ሆኜ እንደማዳምጠው አልጠበቅኩም ነበር።

የንጉሠ ነገሥቱ ዋና ባለሟል የሆነው ወንድሜ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ያልገለጸልኝን፤ ለቤተመንግሥቱ የተለየ ቅርበት አላቸው የሚባሉት ወዳጆቼ ታላላቅ ሰዎች ያልነገሩኝን፤ የእልፍኝ አስከልካዩ መኰንን ደነቀ ይህን ሁሉ ምሥጢር እንዴት ለማወቅ ቻለ? ብዬ ብጠይቅ መልሱን በቀላሉ ማግኘት እንደማልችል እርግጠኛ ሆንኩ። ስለዚህም እንዲሁ ባጭሩ የጃንሆይን የአሠራር ምሥጢራቸውን የማወቅ ዕድል ያላቸው ሚኒስትሮቻቸውና ከፍተኞቹ ባለሥልጣኖቻቸው ሳይሆኑ፤ የእልፍኝ አሽከሮቻቸው ናቸው ብሎ መቀበል የተሻለ መስሎ ታየኝ።

መኰንን ደነቀ የጃንሆይ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ ብዙ የማላውቃቸውን ጉዳዮች ከመንገሩም በላይ፤ እኔንም የንጉሠ ነገሥቱን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ከትልቁ ባለሥልጣን ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር ተነጋግሮ ለማስማማት እንደሚችል የለገሠኝን ቸርነት የማስታውሰው ክፉኛ በመገረም ነው። ሥልጣኔ በቀደመበት አገር፤ ጠቅላይ ሚኒስትሩና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ባልተግባቡበት ጉዳይ፤ የፕሬዚዳንቱ ኤ.ዲ.ሲ (A.D.C) መክሮ አስታረቃቸው ቢባል፤ ግሩም ድንቅ ተብሎ በጋዜጣ ሳይጻፍ አይቀርም ነበር። ይህንን ስል የሰውየውን ችሎታ ለማቃለል ሳይሆን፤ የያዘው ቦታ ይህን ሚና (ሮል) ለመጫወት የሚያበቃው አልነበረም ለማለት ነው። ይልቁንም መኰንን ደነቀ ለዣንዳርመሪ (ለፖሊስ ኃይል) ትምህርት ቤልጊክ አገር የተላከና የአውሮፓንም ሥልጣኔ የጐበኘ ስለሆነ፤ በእሱ ደረጃ ከነበሩት ሰዎች ሁሉ ጥጋበኛ ነው እየተባለ ከመተቸቱ በስተቀር፤ ዘመናዊ አስተያየት ያለው ሰው መሆኑን መካድ አይቻልም። ያም ሆነ ይህ፤ እኔ በጸሐፊ

ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ላይ ምንም ዓይነት ጥላቻ የለኝም። በእኔ ላይ የተለወጡት እሳቸው ናቸው። ይኸውም፤

1ኛ/ በአሜሪካ ጉብኝት ጊዜ በደረሰው የፕሮቶኮል ችግር ምክንያት አስፈላጊ ያልሆነ ዘለፋ ከተናገሩ በኋላ፤ ሁለታችንም ቁጭ ብለን በእርጋታ ሐሳባችንን ተገላልጠን ከስምምነት ላይ በመድረሳችን፤ ከእንግዲህ ወዲህ በመካከላችን ምንም ነገር አይኖርም ብዬ ተስፋ አድርጌ ነበር።

2ኛ/ አዲስ አበባ ከተመለስን በኋላ የጃንሆይ የአውሮፓ ጉብኝት ሲዘጋጅ፤ ምንም እንኳ በአሜሪካው ጊዜ እንዳደረጉት ሁሉ ቢሮዬን ወርሰው፤ የየአገሩን አምባሳደሮች እየሰበሰቡ ፕሮግራሞቹን ሁሉ እኔ ብቻ ልሥራ በማለታቸው ቅሬታ ቢሰማኝም፤ በእኔ ላይ ያላቸው አመለካከት የቀድሞውን መንፈስ የያዘ ስለሆነ ደስ ብሎኝ ነበር።

3ኛ/ መስከረም 1 ቀን 1947 ዓ.ም የኤርትራ ወደ ኢትዮጵያ መቀላቀል ሁለተኛው ዓመት በተከበረበት ዕለት፤ ተድላ ባይሩ ያደረገውን ንግግር አራክሰህ ለውጭ አገር አምባሳደሮች መግለጫ ሰጥተሃል* ተብዬ፤ በጃንሆይና በንጉሣዊው ቤተሰብ ከፍ ያለ ወቀሳ ሲወርድብኝ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ተጋፍጠው የሰጡኝን ድጋፍ መቸውንም አልረሳውም።

4ኛ/ መስከረም 6 ቀን 1947 ዓ.ም እ.አ.አ 16/09/54 ለብዙ ዓመታት አብራኝ ከኖረችው ጓደኛዬ ከፈረንሣዊቷ ከኮሌት ቫላድ ጋር (Colette Valade) የጃንሆይን ፈቃድ አግኝቼ የጋብቻ ውል ሳደርግ፤ ለእኔ ምስክርና ሚዜ ሆነው የፈረሙልኝ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ናቸው። የእኔንና የኮሌትን ግንኙነት ታሪክ ደህና ደድርገው የሚያውቁት ጸሐፊ ትዕዛዝ፤ ችግራችን መፍትሔ አግኝቶ አንድ ቀን ጋብቻችን እንደሚፈጸም ሁልጊዜ ያበረታቱን እንደነበር አልዘነጋውም።

የሕይወት ጓደኛዬ ኮሌት ቫላድ እና እኔ የተዋወቅነው በሊሴ አለክሳንድሪያ ባካሎሪያዬን ተቀብዬ በሶርቦን ዩኒቨርሲቲ የሕግ ትምህርቴን ለመቀጠል ፓሪስ እንደደረስኩ፤ እንደ አውሮፓ አቆጣጠር በመስከረም 1930 ዓ.ም ነበር። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ጋብቻችንን በኦፊሲየል እስከፈጸምንበት እስከ 1954 ዓ.ም ድረስ ለሐያ አራት ዓመታት ሳንለያይ አብረን ኖርን። በሶርቦን ዩኒቨርሲቲ የሕግ ትምህርቴን በማጠናቅቅበት ጊዜ፤ የፖለቲካ ሣይንስ አጥምሬ እንድማርና ዲፕሎም እንዳገኝ፤ ከዚያም በከፍተኛው የንግድ ትምህርት ቤት (H.E.C) ገብቼ እንድመረቅ ሁልጊዜ ከእኔ ሳትለይ ያተጋችኝና የረዳችኝ ጓደኛዬ ነች።

አገራችን በፋሽስት በተወረረች ጊዜ፤ በጃንሆይ ፈቃድ በፓሪስ ያለው የኢትዮጵያ ለጋሲዮን፤ መጀመሪያ በአንደኛ ጸሐፊነት፤ ቀጥሎም ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሩ ብላቴን ጌታ ወልደማርያም ከለቀቁ በኋላ፤ በጉዳይ ፈጻሚነት (Charge D'Affaires) ለአራት ዓመታት ያህል ስሠራ ጓደኛዬ ኮሌት አብራኝ ነበረች። እንደ አውሮፓ አቆጣጠር 1940 ዓ.ም የፈረንሣይ ነፃነት በሂትለር ጀርመን በተጨፈለቀበትና ሙሶሊኒም የዚሁ ተባባሪ በሆነበት ጊዜ፤ በፋሽስቶችና በናዚስቶች

* የኤርትራ ጉዳይ የታሪክ መጽሐፍ ክፍል 6 ምዕራፍ 13 ተመልከት

ተይዤ ከመገደል አምልጬ፤ ፖርቱጋል ለመድረስ እስከቻልኩበት ጊዜ ድረስ፤ ጓደኛዬ ከሌትና ወላጆቿ ያደረጉልኝ ውለታ የሚዘነጋ አይደለም።

ገና በዩኒቨርሲቲ ሳለሁ፤ የእኔ ዋና ዓላማ አገሬ ተመልሼ ይህን የትምህርት ዕድል የሰጡኝን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን በቅርብ ማገልገል መሆኑንና በአገራችን ባሕል ደግሞ አንድ ኢትዮጵያዊ የውጭ አገር ዜጋ ካገባ ከፍተኛ ኃላፊነትን መቀበል እንደማይችል ለወዳጄ ለከሌት እያስረዳሁ አዘጋጃት ነበር። እሷም ችግሩን በመረዳት የምትሰጠኝ መልስ፤ " ... ትልቁ ቁም ነገር በመካከላችን ያለው መተሳሰርና መተማመን ነው እንጂ፤ የዛሬዎቹ መሪዎች ያወጡትን ሕግ፤ የነገዎቹ ሊያሻሽሉት ይችላሉ። ስለዚህ ተስፋችንን ማጠንከር አለብን ... " ትለኝ ነበር።

ቀደም ሲል እንደጠቀስኩት፤ አብረን መሆን ከጀመርን ከሐያ አራት ዓመታት በኋላ፤ ከጓደኛዬ ከከሌት ጋር የሕግ ጋብቻ ለመፈጸም እንዲፈቅዱልኝ ደፍሬ ለጃንሆይ በጽሑፍ አመለከትኩ። ጃንሆይ የእኔን ጉዳይ ከብዙ ዘመን ጀምሮ የሚያውቁት ቢሆንም፤ አንድ ቀን አክሊሉ ሐሳቡን ይለውጥና ከአገሩ ሰው ጋር ትዳር ይመሠርታል የሚል ተስፋ ነበራቸው። አሁን ግን በሐሳቤ የቆረጥኩ መሆኔን ከነምክንያቱ በጽሑፍ ስለምናቸው፤ ጨክነው አይቻልም ማለት አልፈለጉም። ውሳኔ ከመስጠታቸው በፊት፤ ራስ ካሣን አማከሯቸው። ይኸውም የውጭ ጉዳይ ሚኒስትራችን ለብዙ ጊዜ የሚያውቃትን የፈረንሣይ ተወላጅ ለማግባት ፈቃድ ስለጠየቀን ምን ማድረግ ይሻላል? በማለት ነበር። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ እንደነገሩኝ፤ በእኔ ጉዳይ ራስ ካሣ የሰጡትን አስተያየት ሁልጊዜ አስታውሰዋለሁ።

" ... ይኸ ልጅ እኔ ሳየው ከሌሎቹ ሚኒስትሮች ሁሉ አነጋገሩና አኳኋኑ የተለየ ነው። ምናልባት ፈረንጅ አገር እንዲማር ተልኮ ለብዙ ዓመታት እዚያው ማደጉ፤ ከአገራችን ትምህርት እንዲርቅ ሳያደርገው አልቀረም። ወደ አገር ከተመለሰም በኋላ፤ ያንኑ የፈረንጆቹን ጉዳይ በመሥራት እስካሁን በቆየበት ዘመን ወደ አገራችን ልማድ ፊቱን የመለሰና የተቀላቀለ ሆኖ አልታየም። በግል አኗኗሩም እዚያው በፈረንሣይ አገር ካወቃት ሴት ጋር መሆኑ ወሬው ከተሰማ ቆይቷል። አሁንም ከዚቹ ሴት ጋር ጋብቻዬን ለመፈጸም ይፈቀድልኝ ብሎ ያመለከተው፤ ከውጭ ጉዳይ ሥራው ጋር የውጭ ተወላጅ የሆነች ሴት ማግባቱ መንግሥታችንን የሚያሳስብ መሆኑን ተረድቶት ነው። አለበለዚያ ቢጤውን የአገር ሰው ፈልጉ ቢያገባ ኖሮ ፈቃድ መጠየቅ አያስፈልገውም ነበር። ለአገር ጉዳይ ከንጉሥ የተቀበልከው አደራ ብርቱ ምሥጢርንትና ክብደት ስላለው፤ አንተን የሚያህል ሰው ከፈረንጅ ጋር ቤተሰብ መሆን አይፈቀድለትም ተብሎ ቢነገረው፤ እንግዲያው ሹመቱም ሥራውም ይቅርብኝ ብሎ አያመለክትም ወይ? እንደዚህስ ቢጠይቅ መልሱ ምንድን ነው? መቸም በጊዜያችን የፈረንጆቹን ጥበብ መከተል አለብን ስለተባለ፤ በእኛ ልማድ ይቀጣ! ይታሰር! አይባልም። ከዚህ ቀደም በዚያ በመከራው ዘመን ስደትን እንደጀመርን፤ ያ የነሂትለር ወዳጅ በመሆን እኛን ይጠላን የነበረው የእንግሊዝ ንጉሥ፤[*] የምወዳትን የአሜሪካን ሴት በዚህ ላይ ፊት የሆነች፤ ማግባት አትችልም ካላችሁኝ፤ ዘውዱ ያውላችሁ ብሎ አገሩን ለቅቆ ወጣ እየተባለ ሲነገር ትዝ ይለኛል። አሁንም አክሊሉ እንደእቅሙ፤ ከሹመቱም ከክብሩም ፈረንጇ ሚስቱ ትበልጥብኛለች ብሎ ካመረረ፤ የሚሻለው ከሚኒስትርነቱ ማሰናበት ነበር።

---

[*] የተጠቀሰው የእንግሊዝ ንጉሥ ኤድዋርድ 8ኛ ታሪክ ነው።

ነገር ግን ለጊዜው ለሥራው በቶሎ ተተኪ ማግኘቱ የሚያስቸግር ከሆነ፣ በዚህም ላይ እስከአሁን ለብዙ ዓመታት የሰጠው አገልግሎት ፍሬ ያለው ስለሆነ፣ የተለየ አስተያየት አድርጉ ጋብቻውን እንዲፈጽም መፍቀዱ የተገባ ይሆናል። ሆኖም ለቤተመንግሥታችን ታሪክና ክብር ሲባል፣ ንጉሠ ነገሥቱ በሚገኙበት አደባባይ እከሊሉ ፈረንጇን ሚስቱን ይዞ ለመምጣት የተለየ ፈቃድ እስኪሰጠው መቆየት አለበት … "

ይህንን የታወቁትን መስፍን የራስ ካሣን አስተያየት አንድ ቀን ታሪክህን ስትጽፍ ይረዳሃል ብለው የነገሩኝ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ናቸው። ራስ ካሣ በተናገሩት ውስጥ፣ "ቢጤውን ቢያገባ ፈቃድ አያስፈልገውም ነበር" ያሉት፣ ምን ለማለት ነው? ብዬ ጸሐፊ ትዕዛዝን ጠየቅኳቸው።እሳቸው ሲያብራሩልኝ፣ "አንድ ሚኒስትር ትዳር ለመያዝ እማላጅ ልክ የጃንሆይን ፈቃድ የሚለምነው፣ እንደ አንተ ፈረንጅ ለማግባት ከፈለገ ወይም ደግሞ በዘሩ ደሀ ሆኖ ከንጉሣዊ ቤተሰብ ውስጥ ለማግባት ከተመኘ ነው። እስበለዚያ እንደ አንተ ያለ ደሀ ቢጤው የሆነችውን ደሀዋን ፈልጉ ካገባ፣ ፈቃድ አያስፈልገውም። መብቱ ይጠበቅለታል … " ማለት ነው አሉኝ።

በእኔ ጉዳይ ከራስ ካሣ የተሰጠውን አስተያየት ጃንሆይ ስለተስማሙበት፣ በልዩ ጸሐፊያቸው በአቶ ተፈራወርቅ በኩል፣ "ጋብቻህን እንድትፈጽም ፈቅደንልሃል። እሷም ወደ ቤተመንግሥታችን ተጠርታ የምትመጣበት ጊዜ ሲወሰን ወደፊት ይነገርሃል። ለግል ሕይወትህ ያሰብከውን ሁሉ ግዚአብሔር ይባርክልህ" የሚል መልዕክት ላኩልኝ። በዚህ እኔና ኮሌት በጣም ደስ አለን። ዋናው ደስታችን ጋብቻችን በይፋ እንዲታወቅ መፈቀዱ ነው። ኮሌት ለበዓል ሆነ ለግብዣ ወደ ቤተመንግሥት ለመጠራት ጊዜው ደርሶ እስኪፈቀድላት በትዕግሥት ትጠብቃለች። እስከዚያ በየወዳጆቻችን ቤት እንዲሁም በየኤምባሲው ስጋበዝ አብራኝ ትካፈላለች። በዚህ አኳኋን የእኔና የኮሌት ቫላድ ጋብቻ በኢትዮጵያ አቆጣጠር መስከረም 6 ቀን 1947 ዓ.ም በፈረንጆች አቆጣጠር መስከረም 16 ቀን 1954 ዓ.ም በወንድሜ በአካለወርቅ ቤት እጅግ ቀልጣፋ በሆነ ዝግጅት ተፈጸመ።

በዚህ የጋብቻ ውል አፈጻጸም ላይ ምስክሮቼና ሚዜዎቼ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ (ኋላ ጸሐፊ ትዕዛዝ) የጋብቻችን ዳኛ ሆኖ የተሠየመው ኮሎኔል ክፍሌ ዕርገቱ (ኋላ ደጃዝማች) ለእኔ የውል አባት የሆነው አቶ አሥራት ይነሱ (ኋላ አምባሳደር) በኮሌት በኩል ደግሞ፣ የውል አባት አቶ አካለወርቅ፣ ምስክር የፈረንሣይ አምባሳደር ሲገኙ፣ ሁለቱ ወንድሞቼ አቶ መኮንን እና መክብብ አልነበሩም። ለምን ቀሩ? ብዬ አካለወርቅን ብጠይቀው፣ አቶ መኮንን " … ሁለቱ ፈረንጆች ሲጋቡ እኛ ምን እናደርጋለን? … " እያለ ሲቀልድ ነበር። መክብብም እሱን ሲያጅብ ይሆናል አለኝ።

ከፊርማው በኋላ ኮሌትና እኔ ለጥቂቶች ወዳጆቻችን በመኖሪያ ቤታችን ራት አዘጋጅተን ነበር። አቶ መኮንን ግብዣ (በተለይ ማታ) ስለማይቀበል አልጠራሁትም። ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና ከሌሎቹም ወዳጆቻችን ጋር መልካም የሆነ ምሽት አሳለፍን። በማግሥቱ ጠዋት እኔ ቤተመንግሥት ስገባ፣ አቶ መኮንን ሲወጣ አገኘሁት። ከሰላምታ በስተቀር እሱም ጋብቻዬ በመፈጸሙ እንኳን ደስ አለህ አላለኝም። እኔም ለምን ሳትመጣ ቀረህ? ብዬ አልጠየቅኩትም።



አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ ከፈረንሣዊቷ ከማድሚዜል ኮሌት ቫላድ ጋር
ጋብቻቸውን እንደፈጸሙ፤

እንግዲህ! ጃንሆይ ሎንደን በነበሩ ጊዜ የመከሩኝን ፓሪስ ከመጣን በኋላ ደግሞ ጸሐፊ ትዕዛዝ የዛቱብኝን አሁን ደግሞ መኮንን ደነቀ የነገረኝን በአንድነት ሰብስቤ ሳመዛዝን፣ በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና በአቶ መኮንን መካከል ፍቅር ተንዶ ጠብ መጀመሩ በትክክል ተገለጠልኝ። እኔ መቸም የአገራችንን ታላላቅ ሰዎች ጠባይና አስተሳሰብ መረዳት የምችለው ነገር ካለፈ በኋላ ነው። በዚህ በኩል ወንድሞቼ አካለወርቅና መክብብ ይተቹኝ የነበረው ትክክል ነው ብዬ አሰብኩ። በዚህ አኳኋን ወደ ኋላ ተመልሼ ሳሰላስል፣ ሁለት ነገሮች ትዝ አሉኝ።

1ኛ/ ከአሜሪካ ጉዞ በኋላ ለአውሮፓው ጉብኝት እስከመጣንበት ጊዜ ድረስ፣ አቶ መኮንን እና ጸሐፊ ትዕዛዝ እንደ ድሮአቸው በየስብሰባው ሲደጋገፉ አላየኋቸውም። ይኸ አንድ ምልክት ነው ብዬ አሰብኩ።

2ኛ/ የእኔ ጋብቻ ሲፈጸም አቶ መኮንን ያልመጣበት ዋናው ምክንያት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ምስክሬና ሚዜዬ በመሆናቸው፣ አብሮ ለመገኘት ባለመፈለጉ መሆን አለበት፣ እንደዚሁም ጸሐፊ ትዕዛዝ ወንድሜ መኮንን የት ቀረ? ብለው አለመጠየቃቸው በመካከላቸው ችግር መኖሩን የሚያሳይ ተጨማሪ ምልክት ነው።

ይህን ሁሉ በየመልኩ ከመረመርኩና ካጠናሁ በኋላ፣ በእነዚህ በሁለቱ የጃንሆይ ታማኞችና ብዙ ሥልጣን ባላቸው ሰዎች መካከል የተፈጠረውን አለመግባባት ለማስወገድና ለማስታረቅ እንደእኔ የመሰለ ሰው ምንም ዓይነት ተደማጭነት እንደማይኖረው እርግጠኛ ሆንኩ። ሁለተኛ መኮንን ደነቀ እንደሰነዘረልኝ፣ ሁለቱን ታማኞቻቸውን አጣልተው ማለያየት የሚፈልጉት ጃንሆይ ከሆኑ፣ በዚህ ጊዜ እንደ እኔ ያለ ሰው ፀጥ ብሎ ከመቀመጥ በስተቀር በምንም ጉዳይ ውስጥ መግባት እንደሌለበት ከልቤ አመንኩ።

3ኛ/ ፓሪስ ከመጣን በኋላ የኤርትራን ጉዳይ መነሻ አድርገው እኔን ለማበሳጨት ለተናገሩትና፣ ቀጥሎም ከወንድምህ ጋር በእኔ ጀርባ የምትሠሩትን ሁሉ ሰምቻለሁ ብለው ለዛቱት፣ የእኔን አቋም ምንም ሳላስቀር ዘርዝሬ ስለአስረዳኋቸው የሚቆጨኝ ነገር እንደሌለ በራሴ ላይ ሙሉ እምነት አሳደርኩ።

4ኛ/ ከእንግዲህ ወዲህ ጸሐፊ ትዕዛዝ እኔን ተቀይሜሃለሁ የሚሉት ነገር ቢኖራቸው፣ እሳቸው ራሳቸው እንሥተው ካላነጋገሩኝ በስተቀር፣ እኔ ቅድሚያ ወስጄ መጠየቅ የለብኝም ብዬ ወሰንኩ።

ከፓሪስ በኋላ በሌሎቹ በአውሮፓ አገሮች በተደረጉት የረዥም ጊዜ ጉብኝቶች ላይ እና ከዚያም አዲስ አበባ ከተመለስን ወዲህ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝና እኔ የቅያሜውን ጉዳይ እንሥተን አንድም ቀን ሳንነጋገር ወይም ሐሳብ ሳንለዋወጥ እሳቸው ወደ እሩሲ ተዛወሩ።

# ምዕራፍ ፲

# ከአውሮፓ ጉብኝት መልስ የወልደጊዮርጊስና የመኰንን ሀብተወልድ መለያየት

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ታላቋ ብሪታንያንና ፈረንሣይን፣ እንዲሁም ሌሎቹን የአውሮፓ አገሮች በመጐብኘት ሁለት ወራት ከቆዩ በኋላ፣ እንደ ኢ.ት.አቆ. ኅዳር 27 ቀን 1947 ዓ.ም አዲስ አበባ ሲገቡ፣ የተደረገላቸው አቀባበል ከአሜሪካ ጉዞአቸው ሲመለሱ እንደታየው እጅግ የደመቀ ነበር። ከአውሮፕላን ማረፊያው እስከ ታላቁ የአፄ ምኒልክ ቤተመንግሥት ድረስ የተዘረጋው የሕዝብ አቀባበል ሥነ ሥርዓት በሚያስደስት ሁኔታ ከተከናወነ በኋላ፣ በዙፋን አዳራሽ የሻምፓኝ ግብዣ ሲደረግ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከወትሮአቸው የተለየ የቀዘቀዘ መንፈስ አሳይተዋል እያሉ፣ አንዳንድ ተመልካቾች ሲተቹ ተሰምቷል።

በዚሁ ዕለት ወደ ማታ አሥራ አንድ ሰዓት ገደማ ላይ፣ ከዚህ ቀደም ከአሜሪካ ሲመለሱ እንዳደረጉት አቶ መኰንን ሀብተወልድና ባለቤታቸው ወይዘሮ በየነች ምናሴ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን እንኳን ደህና መጡ ለማለት ወደ መኖሪያ ቤታቸው ሄዱ። እንደተለመደው ወንዶቹ በአንድነት ሴቶቹ ደግሞ ለብቻቸው ሆነው ሲጨዋወቱ፣ ከምሽቱ አንድ ሰዓት ሲሆን አቶ መኰንን በድንገት ተነሥተው እንሂድ አሉ። ተሰነባብተው ሲወጡ፣ ወይዘሮ በየነች ከዚህ ቀደም አይቼው የማላውቀው ሁኔታ አጋጠመኝ አሉ። ይህንንም ከብዙ ዓመታት በኋላ አስታውሰው የሚከተለውን አጫውተውኝ ነበር። " ... ለወትሮው ጸሐፊ ትዕዛዝ ቤት በምሽት ከሄድን ራት ሳንጋበዝ አንመለስም። በዚህ ቀን ግን ሁኔታው በጣም ተለዋውጦ ግብዣውም ቀርቶ አየሁ። በተለይ ከቤቱ መውጫ በር ላይ የጸሐፊ ትዕዛዝና የአቶ መኰንን የስንብት ሰላምታ በጣም ቀዘቀዘብኝ። ከመኪናችን ገብተን ስንሄድ፣ አቶ መኰንን ፊታቸውን አጥቁረው አንድ ቃል ሳይተነፍሱ እቤታችን ደረስን። በልማዴ ጌቶችን ደፍሬ የመንግሥት ጉዳይ ጠይቄያቸው አላውቅም። ሁኔታው በጣም ስለአሳሰበኝ፣ ዛሬ ምን ደረሰ? ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር የስንብት ሰላምታ ስትለዋወጡ፣ በሁለታችሁም ላይ የድሮውን ሁኔታችሁን አላየሁም አልኳቸው። ቀና ብለው አዩኝና፣ አዎን ያስተዋልሽው ልክ ነው። ጸሐፊ ትዕዛዝ በጣም ተለውጦ ነው ያገኘሁት። ልብ ባትይው ይሆናል እንጂ፣ ገና እቤቱ ስንደርስ፣ አቀባበሉ በጣም የቀዘቀዘ ነበር። እንዲያውም ጠዋት አውሮፕላን ማረፊያ ሳገኘው ከልማዱ የተለየ ሰላምታ ሰጠኝ። እኔም እስቲ ላስጨርሰው ብዬ ነው እንጂ ዛሬ እቤቱ መሄድ አልነበረብኝም። ለማናቸውም የኛ ሁኔታ እስኪለይለት ድረስ በትዕግሥት መጠበቅ ነው። ሆኖም ዛሬ ጸሐፊ ትዕዛዝ ለእኔ ባሳየኝ መንፈስና በተነጋገርናቸው ጉዳዮች፣ ከእንግዲህ ወዲህ እኔና እሱ ወደ ድሮአችን ወዳጅነት የመመለስ ዕድል የሚኖረን አይመስለኝም ብለውኝ፣ ወደ ጽሕፈት ጠረጴዛቸው አምርተው እንደተለመደው ወረቀቶቻቸውን ማገበብ ጀመሩ። በጣም ደነገጥኩ። በጣምም አዘንኩ። እነዚህ ሰዎች እኮ ወንድማማቾች ነበሩ። እኔ ከመጣሁ አንድም ቀን ተለያይተው አይቼ አላውቅም። ባለቤታቸው ወይዘሮ አልማዝ ይልማም፣ ገና ከድሮው ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር ጋብቻቸው ከሚዘጋጅበት ጊዜ ጀምሮ ከእኔ ጋር በጣም የምንዋደድና በሁሉም ነገር የምንስማማ ነበርን። ወንዶቹ ቢለያዩም እኔ

**መቸም ለወዳጄ ለወይዘሮ አልማዝ ስልክ እየደወልኩ መጠየቁን አላቋርጥም ብዬ ቀጠልኩ። እሳቸውም እንደተመቻቸው አልፎ አልፎ ይደውሉልኝ ነበር። ጨርሶ የተለያየነው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ አሩሲ ተሾሙ ከተባለበት ቀን ጀምሮ ነው ... "**

ወይዘሮ በየነች ምናሴ እንዳሉት፤ ህዳር 27 ቀን 1947 ዓ.ም የወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስና የመኰንን ሀብተወልድ የፖለቲካ ወንድማማችነት መተሳሰሪያ የተቋረጠበት ዕለት ሆኗል። በዚች ኅዳር 27 ምሽት፤ በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ መኖሪያ ቤት የደረሰውን ሁኔታ አቶ መኰንን ሀብተወልድ በያዙት የግል ማስታወሻ ለወንድሞቻቸው የገለጹላቸው የሚከተለውን ነው።

" ... በአውሮፕላን ማረፊያ ጃንሆይ ከአውሮፕላናቸው ወርደው የጦር ሚኒስትሩ ዤኔራል አቢይ እየመራቸው የክብር ዘቡን ለመጐብኘት ሲሄዱ፤ እኔ ወደ ጸሐፊ ትዕዛዝ ሄጄ እንኳን ደህና መጣህ ብዬ ስስመው፤ እንደ ቀድሞው የሞቀ መንፈስ አላሳየኝም። እኔም፤ በጉዞው ላይ ከጌቶቹ ጋር የደረሰ ነገር ይኖር ይሆን? በማለት፤ ያሳየኝ የፊት ማጥቆር ሁኔታ በእኔ ላይ ነው ብዬ አልጠረጠርኩም። ወደ ማታ ከዚህ ቀደም እንዳደረግኩት፤ እንኳን ደህና መጣህ ለማለት በየነችን ይዤ እቤቱ ሄድኩ። እዚያም ሲቀበለኝ መንፈሱ ጨርሶ የድሮው አልነበረም። ወንበር ከያዝኩ በኋላ፤ ታዲያስ! የአሁኑ የአውሮፓው ጉዞአችሁ እንዴት ነበር? .... አልኩት። ስንጐበኘው በከረምነው በሰለጠነው የአውሮፓው ዓለም፤ **"መንግሥትን የሚፈጥረው ሕዝብ መሆኑንና፤ መንግሥትም የሚለፋው ሕዝብን ለማገልገል ብቻ መሆኑን ማየት ምን ያህል እንደሚያስደስት በበቂ አኳኋን ለማስረዳት ያስቸግራል። መቸም በእኛ ዕድሜ አገራችን ለዚህ ዕድል እንደማትበቃ ተስፋ ቆርጬ ተመልሻለሁ። ...** " አለኝ። በዚህ አነጋገሩ በጣም ተገረምኩ። ጥቂት ፀጥ ካልኩ በኋላ፤ አየህ? ጸሐፊ ትዕዛዝ አልኩት። የሰለጠነውን የአውሮፓውን ዓለም ማየት እኮ፤ የመጀመሪያ ጊዜህ አይደለም። ይልቁንም ዘመኑ የመከራ ይሁን እንጂ፤ በዚያ ነፃነታችን በተገፈፈበት ጊዜ፤ ለአምስት ዓመታት ኖረህበታል። ዛሬ እንዳየኸው ፈረንጆቹ ከደረሱበት ደረጃ አገራችን ደርሳ እኛ ልናያት ባንችልም፤ በበኩሌ እኛን የሚተካን ትውልድ የማየት ዕድል አይኖረውም ብዬ አላስብም። ለመሆኑ አንተ፤ ይህን ያህል ተስፋ ያስቆረጠህ ምክንያቱ ምንድን ነው? አልኩት። እሱም መለሰልኝ። የሚተካን ትውልድ የኢትዮጵያን ሥልጣኔ ለማየት የሚበቃው፤ እኛ ዛሬ ለአገር ዕድገት የምንሠራው ሁሉ ፍሬያማ ሲሆን ነው። ነገር ግን በያዝነው አሠራር፤ አገራችን ወደ ሥልጣኔ ጐዳና የሚያራምዳትን መንገድ ይዛለች ለማለት ጨርሶ የሚታሰብ አይደለም። **እኔን ተስፋ ያስቆረጠኝ የዛሬው የመንግሥታችን አሠራር ነው።** አለኝ። እኔም መለስኩና፤ ታዲያ! አንተም ሆንክ እኔ፤ በመንግሥታችን አመራር የጐደለው ምን እንደሆነ፤ የሚሻሻለውም ምንና ምን መሆን እንዳለበት፤ በምንስ አሠራር የአገራችን ሥልጣኔ ሊፋጠን እንደሚችል ለመሪያችን ለማስረዳት ምን የሚከለክለን ነገር አለ ? .... ብዬ ጠየቅኩት። አየህ! አቶ መኰንን ? አለኝ። **አንተ እንደምትለው ለአገር ጠቃሚ የሚሆነውን ሐሳብ ሁሉ እያስተባበርን ፕላን እያዘጋጀን ለማቅረብ፤ የሚያስቸግር ነገር አልነበረም። ነገር ግን መጀመሪያ እኛው ራሳችን እርስ በርሳችን ሳንስማማና ሳንተማመን ምን ዓይነት ፕላን ነው የምናዘጋጀው ?** አሁን የምናደርገው፤ እያንዳንዳችን በየፊናችን ከግል ጥቅማችን ጋር የተያያዘ ሥራ ስለምንሠራ፤ <u>"የቀክከር ቤት ሳይዘጋ ያድራል"</u> **እንደተባለው፤ በእኛ አሠራር ኢትዮጵያ ከድህነቷም ሆነ ከመከራዋ ሳትላቀቅ ሕይወቷን እንደምትገፋ ማወቅ አለብን፤** አለኝ። በዚህ ጊዜ ይህ ሰው ለጠብ ዳር ዳር ማለቱ ተሰማኝ። .... እኔም መልሼ አየህ! ጸሐፊ ትዕዛዝ? አልኩት። አንተና እኔ ለብዙ ዓመታት በትልቅ መተማመን ስንተባበርና ስንሠራ ኖረናል። ከዚህም

የተነሣ ለአገራችን ጠቃሚ የሆኑትን ብዙዎች ሥራዎች ሠርተናል። ዝርዝሩን መደርደር ባያስፈልግም፤ ደህው ወገናችን ከሥቃዩ እንዲላቀቅ ያደረግነው ሙከራ ጥቂት አይደለም። አሁን በጣም የገረመኝ፤ በዚህ በአውሮፓ ጉብኝት ምክንያት በተለያየንባቸው በሁለት ወራት ውስጥ፤ ምን ቢደርስብህ ወደ አዲስ አስተሳሰብና ወደ አዲስ አቅጣጫ አመራህ ? የዚህን ምክንያት ባውቀው ደስ ይለኛል አልኩት። ወዲያው፤ ስማኝ አቶ መኰንን አለኝና፤ <u>ፊቱን አኮማትሮ ያልጠበቅኩትን ተናገረ።</u> ሁለታችን ተማምነንና ተባብረን ለአገራችን ሕዝብ የሠራናቸው ብዙዎች ናቸው ትለኛለህ። ይኸ እኮ የምትናገረው የድሮውን ታሪክ ነው። **የዛሬውን አይደለም። በዛሬው ሰዓት አንተ የቀድሞው ወንድሜ ወዳጄ መኰንን ሀብተወልድ አይደለህም። የዛሬው መኰንን ሀብተወልድ በእኔ ላይ ከተነሡት ጠላቶቼ ጋር ተባብሮ ከመሪያችን ጋር ባለው ልዩ ዓቃቤ ሰዓት እኔን ለማጥፋት የሚጥር መሆኑን ስምቻለሁ። መቸም እግዚአብሔር ይመስገን! ለእኔ የሚቀረቀሩ ብዙዎች ስለሆኑ የማልሰማው የለም።** በተለይ በጣም ያዘንኩት፤ ልጄ ወንድሜ እያልኩ ያሳደግኩት አክሊሉ ሀብተወልድም ከጃንሆይ ጋር በቆይታ እየተነጋገረ በእኔ ላይ ሲዶልት መታየቱ ነው። ይህንንም ለእሱ ለራሱ አሁን በቅርቡ ሎንዶን ላይ በነበርን ጊዜ ገልጬለታለሁ። እሱም የሚወራው ሁሉ እውነት አለመሆኑን በሰፊው ካስረዳኝ በኋላ፤ **በእግዚአብሔር እርዳታ እውነት ተገልጣ እስክትወጣ፤ በትዕግሥት እንድንጠብቃት ሁለታችንም ተስማምተናል።** በሎንዶን እኔ ለአክሊሉ የነገርኩት የፈጠራ ወሬ አይደለም። ከእውነተኛ ቦታ የተገኘውን ነው። ዛሬ ደግሞ ወደፊት እንዳይቆጨኝ ለአንተ ገልጬ የነገርኩህ፤ እኔ የሰማሁትን በሚገባ እንድታውቀው ነው። በእግዚአብሔር ቸርነት፤ **እውነት ተደበቃ አትኖርም። ጊዜ ትወስድ ይሆናል እንጂ፤ ትወጣለች። በዚያን ጊዜ ማንን አሸንፋ፤ ማንን እንደምታነሣ አቅሟን ታሳያለች .....** አለኝ። እኔም እንደዚህ ስል መለስኩለት። የምታስበውንና የሰማኸውን ሁሉ ገልጠህ በመናገርህ አመሰግናለሁ። ከተናገርከውም ውስጥ በጣም ደስ ያለኝ፤ <u>"እውነት ተደብቃ አትቀርም፤ ትወጣለች"</u> ያልከው ነው። እኔም፤ ይህንን ከልቤ የማምንበት ስለሆነ፤ የምቀበለው በደስታ ነው። በሌላው በተናገርከው፤ እጅግ ያሳዘነኝና መንፈሴን የነካው፤ እኔ ከጃንሆይ ጋር ያለኝን የተለየ ዓቃቤ ሰዓት የምጠቀምበት፤ <u>ለአገር ጉዳይ ማከናወኛ ሳይሆን፤ ለሰዎች ጥፋት ነው</u> ብለህ የተናገርከው ነው። እኔ ለዚህ አሳዛኝ ቃል፤ ሐሰት ነው ... ፈጠራ ነው ... እያልኩ ለማስተባበል አልሞክርም። ፈጣሪ ይፍረድብኝ ብዬ ስሜቴን ከመግለጽ በስተቀር ሌላ አልጨምርም። አንተ የማታውቀው ነገር የለም። **እኔ ከጃንሆይ ጋር የተለየ ዓቃቤ ሰዓት እንዲኖረኝ የተመደበው፤ ጃንሆይ ንጉሠ ነገሥት ሳይሆኑ ገና በአልጋወራሽነታቸው ዘመን ነው። ይኸውም፤ የዛሬ ሠላሳ ዓመታት ማለት ነው።** በዚህ ከጃንሆይ በተሰጠኝ ዕድል፤ አገሬንና ወገኖቼን የሚጠቅሙትን ጉዳዮች ከማስፈጸም በስተቀር፤ እንኳንስ **ወዳጆቼን የሚጐዳ፤** ጠላቶቼን **የሚያጠቃ** ነገር **ሠርቼበት እንደሆነ፤ ፈጣሪዬ ፍርዱን እንዲሰጠኝ እለምነዋለሁ።** እኔ በሕይወቴ ለሰው ጥፋት ስጥር አልታይም። ይልቁንስ ! አንተ ነህ፤

**"ከወደድህ መጥቀሙን፤**
**ከጠላህ መጉዳቱን፤**

ታውቅበታለህ እየተባልክ ዝናህ በሰፊው የሚነገርልህ !

እንግዲህ! ነገሬን ለማቆም በእኔ ላይ የሰማኸውን ሁሉ ካመንክበት፤ <u>መቀጠል ትችላለህ።</u> እኔ ግን፤ አንተ ባልከው መሠረት እውነት ተገልጣ ዳኝነቷን እስክትሰጥ፤ በትዕግሥት ከመጠበቅ በስተቀር ሌላ የምከተለው መንገድ የለም፤

አልኩት። እዚህ ላይ ንግግሬን ሳቆም፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ አስተያየቱ ወደ መግባባት መንፈስ ያዘነበለ መስሎ ታየኝ። ስማ! አቶ መኰንን ! አለኝ። እኔ እኮ ማንኛውንም ነገር በሆዬ አምቄ ማኖር ስለማይሆንልኝ፤ ሁሉንም አውጥቼ እዘረግፋለሁ። ዛሬ ለአንተ፤ ከዚህም በፊት ለአክሊሉ የተናገርኩት፤ እውነት ተገልጣ እንድትወጣ ነው። አንተም በዚህ በመስማማትህ ደስ ብሎኛል አለኝ። እኔም ይህንኑ መልካም መንፈስ ለማዳበር ወዲያው ቀጠልኩና ጸሐፊ ትዕዛዝ! ስለ አንተ ከውጭ ወሬ ሰምቼ ሳይሆን፤ እኔው ራሴ አተኩሬ ያየኋቸውን አንዳንድ ነገሮች ብነግርህ የሚሻል ይመስለኛል አልኩት። እሺ ደስ ይለኛል አለኝ።

ባለፉት ስድስት ወራት በመጠኑ አንሥቼብህ ነበር። ዛሬ የምነግርህ ግልጽ በሆነ መንገድ ነው። በሥራ ላይ የምታሳየውን የቁጡና የኃይለኛነት ጠባይ በለሰለሰና በመግባባት መንፈስ ብትለውጠው የሚሻል ይመስለኛል። ብዙ ሚኒስትሮችና በተለይም በቀጥታ የምትመራቸው የሥራ ባልደረቦችህ፤ በአንተ ላይ የሚያሰሙትን ሮሮ መስማት ደስ አይልም። ይህም አያያዝ ተቃዋሚዎችን ስለሚያበረክት፤ አንተን ወደሚጐዳ እንጂ፤ ወደሚጠቅም አቅጣጫ እንደማያዘልቅ እርግጠኛ ነኝ። በተለይ አንተ የምትጥረውና የምትጨነቀው፤ ምንም እንኳ ለአገር ጉዳይና ለሕዝብ ጥቅም አስበህ ቢሆንም፤ ዓላማዬን ከግቡ አደርሳለሁ በማለት ከጃንሆይ ጋር መጨቃጨቅና መዳፈር ውጤት የሚሰጥ መስሎ አልታየኝም። አንተም ሆንክ እኔ፤ አገራችንን ማገልገል የምንችለው፤ የኢትዮጵያን ሕዝብ ከመሳፍንትና ከመኳንንት ጭቆና በማላቀቅ ከግባችን የምንደርሰው፤ ጃንሆይ በሥልጣን ሲያቆዩንና ዕምነታቸውን ሲጥሉብን ነው። አንተም ሆንክ እኔ፤ ጃንሆይ ካልፈለጉን ለምንም ነገር የማንሆን ሰባራ ዕቃ ሆነን የምንቀር ነን .... ብዬ ነገሬን ሳልቀጥል አቋርጦ መልሱን ሰጠኝ። አንተ እኮ ! አለኝ። ጃንሆይን እንደመለኮት እንጂ፤ እንደ ሰው አታያቸውም። እንደ ሰው ጥሩ የሚሠሩት አለ። እንደ ሰው የሚያበላሹትና የሚጐዱት አለ። እኛ በቅን ስናገለግላቸውና ስንረዳቸው፤ እንዳይሳሳቱ ለመጠበቅና የሚያደርጓቸውንም ስሕተቶች እንዲያርሙ ከመናገርና ከማስረዳት መቆጠብ የለብንም። በዛሬው ሰዓት አንተንና እኔን የሚያለያየን ትልቁ ነገር፤ በዚህ በጃንሆይ ጉዳይ ነው። አንተ እሳቸው የሚፈልጉትን ሁሉ አሜን ብለህ ትቀበላለህ። መቀበል ብቻ አይደለም። አይገቡ ገብተህ ትፈጽማለህ። እኔ ደግሞ ተለውጫለሁ። እሳቸው የሚሉትን ሁሉ አልቀበልም።። ጠቃሚ ነገሮችን ለማሠራት ሲፈልጉ በደስታ እታዘዛለሁ። ጉዳት ወደሚያስከትል ጉዳና ሲያዘነብሉ፤ ምክንያቱን ገልጬ አይሆንም እላለሁ። አንዳንድ ጊዜም እንዲሰማቸው "እሻፈረኝ" ብዬ እቢሮዬ ቁጭ ብዬ እውላለሁ። እሳቸው በንጉሠ ነገሥትነታቸው፤ እኔም አገልጋያቸው በሚኒስትርነቴ ይብዛ ይነስ እንጂ፤ በኢትዮጵያ ጉዳይ ኃላፊነት አለብን። ስለዚህም፤ እያንዳንዳችን በየደረጃችን ያለብንን የኃላፊነት ድርሻ መወጣት ካልቻልን፤ እንዲሁ ለስሙ ባለሥልጣኖች እየተባልን መኖራችን፤ ለአገራችን ምን ጥቅም ያመጣል? ... እኔ ይህንን ስናገር ጃንሆይን እንደመድፈር ወይም እንደማስቸገር ሊቆጠርብኝ አይገባም። ባጭሩ የኔ ሐሳብና የኔ ዕምነት፤ ጃንሆይን እንደ ፈጣሪያችን እያመለክን፤ የበለጠ እንዳናሳስታቸውና በዚህም ምክንያት የአገራችን ዕድገት እየተወሳሰበ እንዳይጓተት፤ እኛ ታማኞቻቸው በእውነት ላይ ተመሥርተን እውነቱን እንድንነግራቸው ነው። አንተ ግን እስከ ዛሬ እሳቸው የሚሉትን ብቻ እንደ ቅዱስ ቃል እየተቀበልን የኖርነውን፤ አሁንም መቀጠል አለብን የምትል ከሆነ፤ እንደ ቀድሞው አንተና እኔ አብረን መሥራት፤ አብረን መቆም አንችልም አለኝ። እኔም ሳላመነታ፤ ወዲያውኑ የማስበውን ገለጥኩለት። ... እስከ ዛሬ ድረስ ይኸው አሥራ አራት ዓመት ሊሆነን ነው። አንተንና እኔን ያቀራረበንና እንደ ወንድማማች ሆነን ያስተባበረን ጃንሆይን ይዘን፤ የጃንሆይን ዕምነትና ድጋፍ አግኝተን፤ ወገኖችን

የኢትዮጵያን ሕዝብ ከመሳፍንት አገዛዝ ለማላቀቅ እንችላለን ብለን ነው። በዚህ መሠረት፣ አንድነታችንን አጠንክረን በብርቱ በመሥራት ጠላቶቻችንን ሁሉንም ባይሆን ብዙዎቹን አሸንፈናል። የአገራችንንም አስተዳደር በብዙ ረገድ ለማሻሻል ሞክረናል። እንግዲህ ፤ በዚህ ዘዴያችንና በዚህ ጥረታችን፣ ብዙ ጠቃሚ የሆኑ ሥራዎችን ስንፈጽም ከኖርን በኋላ፣ ዛሬ እኔ ጃንሆይን እንደ ፈጣሪ ስማፀናቸው፣ አንተ እንደሰው እንደምታያቸው የተናገርከው እጅግ አስገርሞኛል። ለመሆኑ፣ ከመቼ ጀምሮ ነው አመለካከትህ በዚህ ዕምነት ላይ የተመሠረተው ? ደግሞስ፣ አንተ ለአገራችን መሻሻል ያለህ ሐሳብ ከእሳቸው የፈጠነና ከእሳቸው የተሻለ ሆኖ፣ እሳቸው እንቅፋት ሆነው እንዳትሠራ ያገዱህ መቼ ነው ? ... እስከ ዛሬ ድረስ እኔ እስከማውቀው፣ አንተና እኔ በሰፊው አጥንተን፣ በሰፊው ተከራክረን፣ ከስምምነት ላይ የደረስንባቸውን ጉዳዮች ስናቀርብላቸው፣ አንድም ጊዜ አልቀበልም ብለው ሲያስቸግሩን አልታዩም። ስለዚህ፣ ዛሬ ምን ደርሶብን ነው ከጃንሆይ ጋር ሙግት መግጠም የሚያስፈልገን? እንደምታውቀው፣ እንደ ኢትዮጵያ በመሰለው አገር በመሪና በአገልጋይ መካከል ሙግት ሲፈጠር፣ ፍጻሜው ጠብ ነው። ጠብ ሲደርስ ደግሞ አሸናፊው መሪው ነው። ተሸናፊው አገልጋይ ደግሞ መጨረሻው የትም ወድቆ መቅረት ነው። ቀደም ብዬ ነገሬሀለሁ። ለአንተና ለእኔ ዋስትናችን ጃንሆይ ብቻ ናቸው። አንተና እኔ ጃንሆይን ካጣን፣ በሥራ ዓለም ቦታ አይኖረንም። ጃንሆይ ግን እኛን ቢያጡ፣ ሌሎች ተክተው መቀጠል ይችላሉ። .... እንግዲህ፣ የመጨረሻውን ሐሳቤን ልንገርህ ! ይህንን የመጨረሻ ሐሳብ የምለውን፣ ቀድሞ የነበረኝን ለማጠናከር እንጂ፣ አንተ የማታውቀው አዲስ ነገር ነው ብዬ አይደለም። <u>እኔ የማምነው ከፈጣሪዬ ቀጥሎ በጃንሆይ ብቻ ነው።</u> ለአገሬና ለወገኖቼ የአቅሜን መሥራት የምችለው፣ የጃንሆይን ድጋፍና የጃንሆይን ቸርነት ይዤ ነው። እንኳንስ ወዳጆቼ፣ ወንድሞቼም ሆኑ ልጆቼ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አይበልጡብኝም። ስለዚህም፣ ትናንት የጀመርኩትን፣ በሕይወት እስካለሁ ድረስ እቀጥልበታለሁ። ዛሬ በእኔና በአንተ መካከል ልዩነት የተፈጠረብንና ወደ መራራቅ የሚገፋፋን፣ ስለ ጃንሆይ ያለን አቋም ከሆነ፣ አንተ ተለውጠሃል። እኔ እነበርኩበት ቀርቻለሁ። እንግዲህ ! ሁለታችንም በየመንገዳችን መልካሙን እግዚአብሔር ይምራን ..... " ብዬ ተነሥቼ ከቤቱ ወጣሁ፣ <u>ይላሉ አቶ መኰንን ሀብተወልድ።</u> "እንድታዩት" በሚል መነሻ ለወንድሞቻቸው ከሰጧቸው ማስታወሻ ላይ የተወሰደ።

እንግዲህ፣ ለዐሥራ አራት ዓመታት የፖለቲካ አንድነታቸውን አስተሳስረው፣ መሳፍንትንና መኳንንትን በመቋቋም፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ያነቃንቁ የነበሩት እነዚህ ሁለት የድሀ ወገኖች ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ፣ ባልተጠበቀና ባልታሰበ ሰዓት መለያየታቸው ምን ያህል እንደሚያሳዝን መገመት ይቻላል። በዚያች በማክሰኞ ኅዳር 27 ቀን 1947 ዓ.ም ምሽት ሁለቱ ወዳጆች ለጃንሆይ ስለሚሰጡት አገልግሎትና ከጀንሆይ ጋር ስለሚኖሯቸው ግንኙነቶች የሚያስቡትን ከተገላለጹ በኋላ መግባባት ስለአቃታቸው፣ ሁለቱም በየዕምነታቸው መለያየትን ሲወስኑ፣ አንድ ቀን ወደ ቀድሞው ፍቅራቸው ለመመለስ ተስፋ ያደረጉ አይመስልም። ታሪኩን ተከትለን ስንጓዝ፣ በመጨረሻቸው ምን እንደደረሰ እናያለን።

# ምዕራፍ ፯

## የጃንሆይና የወልደጊዮርጊስ ግንኙነት እየሻከረ ሄደ

የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትሩ በቀን ማስታወሻቸው ላይ እንደጠቀሱት፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ያላቸው ግንኙነት ዳመና ጥሎበት ያዩት ከአሜሪካ ጉዞ መልስ እንደ ኢት.አቆ. ከሐምሌ 1946 ዓ.ም ጀምሮ ነው ብለዋል። በዚህ መጽሐፍ ክፍል 8 ምዕራፍ 2 ላይ እንደተጻፈው፣ ከገነተ ለዑል ቤተመንግሥት ሹማምንት በተገኘው መረጃ፣ ስለ ወልደጊዮርጊስ ሥልጣን አሥጊነት በጃንሆይ ሰብሳቢነት የዘውድ ምክር ቤት የምሥጢር ጉባኤ ካደረገ በኋላ፣ በእጅሬ ላይ እርምጃ ለመውሰድ የንጉሠ ነገሥቱ የአሜሪካና የአውሮፓ ጉዞዎች እስኪጠናቀቁ መቆየት ይሻላል ተብሎ መወሰኑ ይታወሳል። ይህ ውሳኔ ጥብቅ በሆነ ምሥጢር እንዲያዝ በመደረጉ፣ ምናልባት ጸሐፊ ትዕዛዝ የአሜሪካው ጉዞ ከመጀመሩ በፊት፣ የዘውድ ምክር ቤቱ በእሳቸው ላይ የመከረባቸውን አልሰሙም ይሆናል። ነገር ግን፣ ንጉሠ ነገሥቱ በጽሕፈት ሚኒስትራቸው ላይ አስተያየታቸው ለመለወጡ አንዱ ማስረጃ፣ አሜሪካንን በኦፊሲየል በጐበኙበት ወቅት፣ በፕሮቶኮል አቀማመጥ አሜሪካኖቹ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ በታች ሲያደርጓቸው፣ ጃንሆይ ይሁን ብለው መቀበላቸው ነው። ይሁን እንጂ፣ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴና በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ መካከል ያለው ግንኙነት እየሻከረ ወደመለያየት ማዘንበሉ በአካባቢው ሊታወቅ የቻለው፣ የአውሮፓው ጉብኝት ከተፈጸመ በኋላ፣ እንደ ኢት. አቆ. ከኅዳር 27 ቀን 1947 ዓ.ም ጀምሮ ነው።

**ለዘጠኝ ዓመታት የግርማዊነታቸው ዋና የእልፍኝ አስከልካይ የነበሩት ብ.ጄኔራል መኰንን ደነቀ ለዚህ መጽሐፍ ደራሲ ስለ ጉዳዩ የሚያውቁትን ከዚህ እንደሚከተለው ገልጸውለታል።**

**" ..... በአውሮፓ የሚደረገው ጉብኝት ተፈጽሞ በኅዳር 1947 ዓ.ም አዲስ አበባ ከተመለስን በኋላ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከቅርብ ወዳጆቻቸው ማንንም ሳያማክሩ በገዛ ፈቃዳቸው፣ ጃንሆይን የበለጠ ቅር የሚያሰኝ ሁለት ዓይነት እርምጃዎች ወሰዱ።**

1/ ከአንግዲህ ወዲህ ጃንሆይ ካልጠሩኝ በስተቀር ከንጉሠ ነገሥቱ ጽሕፈት ቤት "አምሳለ ገነት" አልመጣም አሉ።

2/ ሚኒስትሮቹ በየዓቃቤ ሰዓታቸው አምሳለ ገነት እየመጡ ለጃንሆይ የሥራ ጉዳያቸውን በሚያቀርቡበት ጊዜ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ እኔ መገኘት የለብኝም ብለው፣ ከአምስት ዓመታት በላይ ይከተሉት የነበረውን ፕሮግራም አቋረጡ።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ጃንሆይን ሳያማክሩ ወይም ሳያስፈቅዱ እነዚህን እርምጃዎች በራሳቸው ፈቃድ ብቻ በመውሰዳቸው፣ እኔን ወዳጃቸውን በጣም ስለአሳሰበኝ፣

አስተያየቴን ልነግራቸው ይገባል ብዬ በቀጠሮ እቢሮአቸው ሄድኩ፡፡ እባክዎ? ጸሐፊ ትዕዛዝ የመጣሁበትን ጉዳይ እንድናገር ይፍቀዱልኝ አልኳቸው፡፡ ተናገር አሉኝ፡፡

"..... እኔ እንደማየው ከጃንሆይ ጋር ያለዎት ግንኙነት ከዕለት ወደ ዕለት መሻከሩ ብቻ ሳይሆን ወደ ጠብ እያመራ መሄዱ ሥጋት ላይ ጥሎኛል፡፡ በእርስዎም በኩል ይህንን ለማሻሻል የሚደረግ ሙከራ አላይም፡፡ የጉዳዩ መጨረሻው ጠብ ቢሆን፣ ጥቅሙ ምንድን ነው? ብዬ የመጀመሪያ ጥያቄ አቀረብኩላቸው፡፡ " .... እንደምታውቀኝ እኔ አንድ ታማኝ አገልጋይ የሆንኩ ደሃ ነኝ፡፡ ከንጉሥ ጋር ጠብ ፈላጊ አይደለሁም፡፡ እኔን ለማጥቃት የጠብ ምክንያት የሚፈልጉት ጃንሆይ ናቸው፡፡ አንተ ደህና አድርገህ ታያለህ፡፡ በአሁኑ ሰዓት ጃንሆይ እኔን እያራቁ እኔን ቸል እያሉ፤ እነ መኰንን ሀብተወልድን፣ እነ ራስ አበበ አረጋይን፣ እና ሌሎቹንም እያቀረቡ በእኔ ላይ ኃጢአት ተፈልጐ እንዲዘጋጅ የሚያደርጉት ራሳቸው ጃንሆይ ናቸው፡፡ እንደምታውቀው እኔ ለእሳቸው መንግሥት እንኳንስ ራሴን፤ ቤተሰቤን ጭምር የሠዋሁ ነኝ፡፡ በአገርና በእሳቸው ላይ የደረሱትን መከራዎችና ፈተናዎች ሳልለያቸው አብሬአቸው የተቀበልኩ ነኝ፡፡ ዛሬ ይህ ሁሉ አልፏል፡፡ ነፃነታችን ከፋሽስት ቀንበር ተመልሷል፡፡ ከእንግሊዞች የኮሎኒ ጫና ተላቀናል፡፡ ኤርትራ ተመልሳ ግዛታችን የጥንቷ ኢትዮጵያ ሆናለች፡፡ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የመላዋ ኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትነታቸው ተረጋግጧል፡፡ ስለዚህ፤ ጃንሆይ የሚፈልጉት ሁሉ ስለተሟላላቸው፤ በዛሬው ሰዓት ወልደጊዮርጊስ አያስፈልጋቸውም፡፡ እነ መኰንን ሀብተወልድ፣ እነ አበበ አረጋይ፣ እነ አክሊሉ ሀብተወልድ ይበቋቸዋል፡፡ .... " አሉኝ፡፡ ..... የለም ጸሐፊ ትዕዛዝ! የሚናገሩት ሁሉ ትክክል አለመሆኑን በወዳጅነቴ ደፍሬ እንዳስረዳዎ ይፍቀዱልኝ አልኳቸው፡፡ ጃንሆይ በመሪነታቸው አንዳንድ ጉድለት ቢኖራቸውም፤ የእርስዎን አገልግሎት ሚዛን ላይ አይጥሉትም፡፡ ይልቁንም በቅርቡ እኔ ራሴ ያየሁትን ልንገርዎ! በጃንሆይ ላይ የተለወጡት እርስዎ ነዎት፡፡ ጃንሆይ ሲናገሩ፤ እንደድሮዎ በትህትና እያዳመጡ ጉዳዩን በዘዴ ማስተካከሉን ትተው፤ በአነጋገር መቃወሙን አጠንክረውታል፡፡ እኛ በእልፍኝ አሽከርነታችን ቆመን እንደምናየው፤ እርስዎ አይለው እሳቸው ለስልሰዋል፡፡ ከዚህ ሌላ ደግሞ ያለልማድዎ ጃንሆይ ካልጠሩኝ እቢሮአቸው አልሄድም፡፡ በሚኒስትሮች ጓቃቤ ሰዓት ላይ አልገኝም ብለው ወስነዋል፡፡ የጃንሆይ አዲሶቹ ታማኞች ተዘጋጅተው ስለሚጠብቋቸው እነሱ ይረዷቸዋል የሚል ምክንያት መስጠትዎ ታውቋል፡፡ እኔ በወዳጅነቴ የማውቀውንና የሚሰማኝን ለርስዎ ከመግለጽ ወደ ኋላ አልልም፡፡ በአሁኑ ሰዓት እርስዎ ከማንም ጋር በመጣላት የጠላቶችዎን ቁጥር ማብዛት አይጠቅምዎትም፡፡ ጠንካራ ሠራተኛና ኃይለኛ በመሆንዎ፤ በዛሬው ሰዓት ከገዥዎችም፣ ከሚኒስትሮችም እርስዎን የሚቃወሙት ብዙዎች ናቸው፡፡ ንጉሣውያን ቤተሰቡም፤ የዘውድ ምክር ቤት አባሎችም፤ "እኛን አይወደንም" እያሉ ሌት ተቀን በእርስዎ ላይ ነገር ሲጭሩ ያድራሉ፡፡ አሁን ደግሞ ጃንሆይ ሲጨመሩ፤ እርስዎ ብቻዎን መቅረትዎ አይሆንም ወይ? ከአቶ መኰንን ሀብተወልድም ጋር መለያየታችሁ በጣም አሳስቦኛል፡፡ ሽማግሌ ገብቶ ብትነጋገሩና ብትስማሙ የሚሻል ይመስለኛል፡፡ አቶ መኰንን ብልህነታቸው ለክፉም ለደጉም ስለሆነ፤ ለፍቅራቸው እንጂ ለጠባቸው ዕድል መስጠት አያስፈልግም፡፡ እዚህ ላይ አክሊሉን መጨመርዎ ልክ አይደለም፡፡ አክሊሉ የዋህና ፈረንጅ ነው፡፡ አንድ ምሳሌ ብነግርዎ ይበቃ ይሆናል፡፡ ፓሪስ በጉብኝት ላይ በነበርን ጊዜ፤ (ባለፈው ጥቅምት) እርስዎ በአክሊሉ ላይ ፊትዎን እንዳጠቆሩበት አዝኖ ነገረኝ፡፡ እኔም አጋጣሚውን በመጠቀም፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ጸሐፊ ትዕዛዝን ከጃንሆይ ጋር ለማጣላት ይጥራሉ እየተባለ ይወራል፡፡ እውነቱ እስከየት እንደሆነ የደረስኩበት ነገር የለም፡፡ ለማናቸውም አንተ ቀስ ብለህ ይህ የሚወራባቸው በጣም መጥፎ መሆኑን አስረዳቸው፡፡ ከአንተ ቢሰሙት ይሻላል አልኩትና በእኔ በኩል አንተንና ጸሐፊ

ትዕዛዝ ለማግባባት ቃል እሰጣለሁ ብዬው ተለያየን። አዲስ አበባ እንደተመለስን፣ አክሊሉ አቶ መኰንንን ይፈልግና፣ አንተ ነህ እሱ ጸሐፊ ትዕዛዝን ከጃንሆይ ጋር የምታጣላ፣ ብሎ ይጮሃል። አቶ መኰንን ማን ነገረህ? ይሉታል። ወዳጄ መኰንን ደነቀ ነው ይላቸዋል። እሳቸው ደግሞ እኔን ጠርተው፣ እስቲ ንገረኝ፣ እንዴት ነው? ጸሐፊ ትዕዛዝን ከጃንሆይ ጋር የማጣላው? ብለው ጠየቁኝ። እኔም አስረዳኋቸው። ለአቶ አክሊሉ የነገርኩት፣ አቶ መኰንን በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ ደግ አይሠሩም እየተባለ የሚወራውን እርስዎ እንዲያውቁት በማሰብ ነው ብዬ መለስኩላቸው። እንግዲህ እዚህ ላይ የአክሊሉን የዋህነት ይመልከቱት። እሱ ራሱ በርስዎ ላይ በሚጠነሰሰው ተንኮል ተካፋይ ቢሆን ኖሮ፣ ይህን አያደርግም ነበር። አሁን ዋናው ቁም ነገር፣ ያለንበት ሰዓት በጣም መጥፎ መሆኑን በማየት ለመልካሙና ለሰላሙ ጥረት ማድረግ ነው። ስለዚህ፣ በእኔ በወዳጅዎ አስተያየት፣

1ኛ/ ከጃንሆይ ጋር ግንኙነትዎን እነበረበት ቦታ ይመልሱት፣ ለዚህም ጥበቡም ችሎታውም ስላለዎት፣ ያስቸግርዎታል ብዬ አላስብም፣

2ኛ/ በሚኒስትሮቹ ዓቃቤ ሰዓት ላይ እየተገኙ፣ ከብዙ ዓመታት ጀምሮ ጃንሆይን በመርዳት የሚሰጡትን አገልግሎት ይቀጥሉ፣

3ኛ/ ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ ጋር የነበራችሁን መግባባትና መተባበር ምንም እንኳ ጃንሆይ የማይወዱት ቢሆን፣ ለራሳችሁና ለወገኖቻችሁ ስትሉ መቀጠል አለባችሁ። በመካከላችሁ የታመነ ሽማግሌ ቢገባበት ጥሩ ነው።

ብዬ ከልቤ የማስበውንና የማምንበትን ነገርኳቸው። እሳቸው ግን የሰጡኝ መልስ፣ እንደጠበቅኩት አላረካኝም።

" .... አየህ፣ ኮሎኔል እሉኝ። በቤተመንግሥቱ ካላችሁት ዋና ዋና ሹማምንቶች፣ እኔ የማምናችሁና ወዳጆቼ የምላችሁ፣ አንተንና አዛዥ ተረፈ ወልደገብርኤልን ነው። አባ ሐና አሸርሻሪ ሆነው አይቻቸዋለሁ። ሌሎቹም እሞቀበት አለን የሚሉ ናቸው እንጂ፣ ለቁም ነገር የሚታመኑ አይደሉም። አሁን አንተ ያቀረብክልኝ ሐሳብ፣ እኔን ለመርዳትና ለእኔ ከመጨነቅ የተነሣ መሆኑን አውቃለሁ። የተናገርከውንም ደህና አድርጌ አድምጫለሁ። በበኩሌ የሚመስሉኝን አስተያየቶች ልገልጽልህ እፈልጋለሁ። በመጀመሪያ ከጃንሆይ ጋር ግንኙነትህን አሻሽል ብለኸኛል። አንተ እንዳልከው፣ ከልማዴ ተዛንፌ፣ በአነጋገሬም ሆነ በአቀራረቤ በምወዳቸው ጌታዬ ላይ ተለውጬ ወደ ድፍረት አዘንብዬ እንደሆነ፣ ማረም አለብኝ። ሌላው፣ ከጃንሆይ ጋር የነበረህን ባለሟልነት ዘዴውና ጥበቡ ስላለህ፣ እቦታው መልሰው ትለኛለህ። እኔ በኤክስፔርያንስ እንዳየሁት፣ የጃንሆይ ባለሟል ለመሆን ልዩ ልዩ ጥበብ ያላቸው አጭበርባሪዎች እነማን መሆናቸውን አንተና እኔ እናውቃቸዋለን። እስከ ዛሬ እኔን ከጃንሆይ ጋር ያቀራረበኝ፣ መጀመሪያ ሥራዬ ነው። ቀጥሎ፣ ዘወትር የምነግራቸው ሁሉ "እውነት" የሆነ፣ የማቀርብላቸው ሐሳብ ሁሉ "እውነት" ላይ የተመሠረተ በመሆኑ ነው። እንደምታውቀው፣ ጃንሆይ በእኔ ላይ መለወጣቸው በግልጽ ይታያል። ሁሉም ሰው አውቆታል። ስለዚህ፣ አንድ ቀን እሳቸው የጀመሩት የተገባ አለመሆኑን አይተው፣ እንደድሮአቸው ሊያቀርቡኝ ይችሉ ይሆናል ብዬ ተስፋ አደርጋለሁ። በተረፈ፣ እኔው ራሴ እንደ አጭበርባሪዎቹ ወደፊት "ባለሟል" የምሆንበትን ጥበብ ተምሬ፣ ፕላን አዘጋጅቼ ለመሞከር፣ አእምሮዬ አይታዘዝልኝም። ስለዚህ፣ ጃንሆይ



የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የቅርብ ወዳጆች፡፡
ከግራ ወደ ቀኝ ፊታውራሪ ፀሐዩ እንቆሥላሴ (ኋላ ደጃዝማች) ኮሎኔል መኰንን ደነቀ (ኋላ ብ/ጄኔራል)፡፡

አስፈልጓቸው እኔን እንደቀድሞአቸው የሚያቀርቡበት ቀን እስከሚመጣ መጠበቅ ነው። ከዚህም አያይዘህ፤ በሚኒስትሮች ዓቃቤ ሰዓት ላይ እየተገኘሁ እስከዛሬ ለጃንሆይ ስሰጥ የነበረውን አገልግሎት እንድቀጥል ጠይቀኸኛል። ምናልባት አላስተዋልከው ይሆናል እንጂ፤ በዚህ በሚኒስትሮች ዓቃቤ ሰዓት ላይ የእኔ የወልደጊዮርጊስ አለመገኘት በጣም ያስደሰተው፤ ሚኒስትሮቹን ብቻ ሳይሆን፤ ጃንሆይንም ጭምር ነው። አንዳንዶቹ ሚኒስትሮች ሠራተኛ ለመምሰል የሆነ ያልሆነውን ሠርተናል እያሉ፤ ለጃንሆይ የሚያቀርቡትን የማታለያ ራፖር እኔ እየፈለፈልኩ ቅጥፈታቸውን ስለማገኝባቸው፤ ምን ያህል እንደሚጠሉኝ ታውቃለህ። ጃንሆይ ደግሞ፤ ወልደጊዮርጊስ የሚሰጠውን አስተያየት እየተቀበሉ ከማጽደቅ በስተቀር፤ ምንም ሥልጣን የላቸውም እየተባለ የሚነዛው ወሬ እንዳናደዳቸው ለሁላችንም ግልጽ ነው። ስለዚህ፤ እሳቸው የፈለጉትን ለመወሰን እንዲችሉ የእኔ አለመኖር ያስደስታቸዋል እንጂ፤ ቅር አያሰኛቸውም። እንግዲህ፤ የእኔ በዓቃቤ ሰዓት ላይ አለመገኘት የሚያረካው፤ ጃንሆይንም፣ ሚኒስትሮቹንም ስለሆነ፤ ያደረግኩትን ውሳኔ አልመለስበትም ብዬ ቆርጫለሁ። ሌላው በሦስተኛ ደረጃ፤ ከመኰንን ሀብተወልድ ጋር ዕርቅ ያስፈልጋል ያልከው ነው። መጀመሪያ እኔና እሱ በሐሳብ ተለያየን እንጂ፤ በግላችን አልተጣላንም። ስንገናኝም እንደድሮአችን የጦፈ ባይሆንም፤ ሰላምታ እንለዋወጣለን። እርግጥ ነው! አንተም እንደምታውቀው ጃንሆይ በእኔ ላይ የተለወጡት መኰንን ሀብተወልድ በእኔ ላይ የሚያቀርብላቸውን የተንኮል ራፖር እያዳመጡ ነው የሚል ከሁነኛ ሰው የተገኘ ወሬ ሰምቻለሁ። ወደ አውሮፓ ጉዞ ከመጀመራችን በፊት፤ ጃንሆይ ስለ እኔ ጉዳይ ከመኰንን ሀ.ወ፣ ከአክሊሉ ሀ.ወ፣ ከሣህሉ ድፋዬ ጋር በቆይታ ይነጋገሩ እንደነበረ ሰምቻለሁ። ራስ ካሣ፣ ራስ አበበ፣ ቢትወደድ መኰንን፣ ቢትወደድ አንዳርጌ የጉዳዩ ተካፋዮች ነበሩ ተብሏል። ለማናቸውም ይህ ሁሉ ትርምስ ምን ውጤት እንደሚያስገኝላቸው አላውቅም ብዬ ነገሩን ትቸዋለሁ። ከመኰንን ሀብተወልድ ጋር በሐሳብ ተለያይተናል ያልኩህ፤ በጃንሆይ ጉዳይ ነው። እኛ ሁላችንም እስከ ዛሬ ድረስ ጃንሆይን ስንጎዳቸው የኖርነው አንድ ትልቅ ነገር አለ። <u>የሚፈርዱት፣ የሚወስኑት፣ በጠቅላላው የሚሠሩት ሁሉ ትክክል ነው እያልን እንደ ፈጣሪ የምናመልካቸውና የምንደልላቸው፤ ለራሳቸውም ሆነ ለአገራችን ትልቅ በደል ነው። ስለዚህ፤ በመጀመሪያ እኛው ራሳችንን በራሳችን እርመን፤ ጃንሆይን ለመርዳት ቆርጠን መነሣት አለብን</u>። ይኸውም፤ የመሪነት ክብራቸውን እየጠበቅን፤ በአገር አስተዳደር ጉዳይ ግን ክፉና ደጉን፤ ስሕተቱንና ትክክሉን እየለየን፤ እውነቱን በግልጽ እየነገርን ብንረዳቸው፤ ለአገራችንና ለሕዝባችን ብዙ ጠቃሚ ነገሮች መሥራት እንችላለን ብዬ ሐሳቤን ብገልጽለት፤ አንተ ተለውጠሀል፤ እኔ በነበርኩበት እቀጥላለሁ ብሎኝ ተሰነባብተናል። ስለዚህ የመኰንን ሀብተወልድን ጉዳይ እንተወው። ከእንግዲህ ወዲህ እኔም ከእሱ ጋር እንደድሮው ለመሥራት፤ እሱም ከእኔ ጋር ለመተባበር የምንችል አይመስለኝም። በመጨረሻ፤ አቶ መኰንን የተናገረኝን አስታውሳለሁ። አንተም በመንገድህ፤ እኔም በመንገዴ ብሎኝ ነበር። እውነቱን ነው። ከእንግዲህ ወዲህ መሆን ያለበት እሱ እንዳለው በየመንገዳችን መጓዝ ነው። ስለ አክሊሉ ሀብተወልድ የነገርከኝ ትክክል ነው። እሱ ጠባዩ የፈረንጅ ስለሆነ፤ የአገራችን ተንኮል አይገባውም። ከእሱም ጋር በሎንዶን ተገላልጠን ተነጋግረናል። አካለወርቅ እስካሁን ምንም አልሰማሁበትም። እኔ እስከማውቀው ንጹሕ ሰው ነው። መክብብ ዳምጤ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ዲክታተር ነው እያለ በግልጽ ከመንቀፍ በስተቀር የተንኮል ሥራ የለውም ... " በማለት ላቀረብኩላቸው ሐሳብ መልሱን ሰጡኝ።

## የጄኔራል መኰንን ደነቀ የማጠቃለያ አስተያየት

" ... ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በጽሕፈት ቤታቸው ተቀብለውኝ በር ተዘግቶ ብቻችንን በረዥሙ እነዚህን ሐሳቦች ከተለዋወጥን በኋላ፤ ወደ ቢሮዬ ስመለስ በጣም አዘንኩ። ሐዘኔም፤ ወዳጄ ጸሐፊ ትዕዛዝ ያላቸው ሐሳብና የሚከተሉት መንገድ የሚጐዳቸው እንጂ፤ የሚጠቅማቸው ሆኖ ስላልታየኝ ነው። ጸሐፊ ትዕዛዝ ብዙ ጥሩ ነገሮች ያሏቸው ሲሆን፤ ድክመታቸው የራሳቸውን እንጂ፤ የሌላ ሰው ሐሳብ አለመቀበላቸው ነው። በተፈጥሮ ደፋርና ልበ ሙሉ በመሆናቸው፤ የጠላቶቻቸው ብዛት አያሠጋቸውም። ንጉሣውያን ቤተሰብ እቴጌም ጭምር፤ በራስ ካሣ መሪነት የዘውድ ምክር ቤት አባሎች ተቃዋሚዎቻቸው ናቸው። ከሚኒስትሮችና ከጠቅላይ ገዥዎች መካከል አብዛኛዎቹ ከወልደጊዮርጊስ ሥልጣን ይገላግለን እያሉ የሚጸልዩ ናቸው። ከአርበኞቹም ወልደጊዮርጊስ የሚያደሉት ለስደተኞች ነው በማለት፤ አብዛኛዎቹ የሚማረሩ ናቸው። እንግዲህ ለጸሐፊ ትዕዛዝ የሚቆምላቸው የትኛው ወገን ወይም የትኛው ድርጅት ነው? ብዬ ሳስብ፤ በእኔ በኩል ምንም ነገር አላይም። እርግጥ፤ ከአንዳንዶቹ ጓደኞቼ ጋር ስንጨዋወት፤ የጦር ሚኒስትሩን ጄኔራል አቢይን፣ ከአገረ ገዥዎች እነ ፊታውራሪ ፀሐዬ ዕንቁሥላሴን፣ ከሚኒስትሮች አካባቢ እነ ኮሉኔል ክፍሌ ዕርገቱንና ታምራት ይገዙን የጸሐፊ ትዕዛዝ ወዳጆች አድርገን እንቆጥራለን። ከእነዚህ ውስጥ እኔም አንዱ ነኝ። ነገር ግን ሁላችንም ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የምንወድና የምናደንቅ ብንሆንም፤ ከጃንሆይ ጋር ሲጣሉ ከእሳቸው ጋር እንቆማለን ማለት አንችልም። እዚህ ላይ እውነቱን መናገር ያስፈልጋል። ጸሐፊ ትዕዛዝ ቢሻሩም ቢጋዙም፤ እናዝናለን ከማለት በስተቀር ከሚደርስባቸው ቅጣት ወይም ሽረት ልናድናቸው አንችልም። የአገራችን ጉዳይ በጣም አስቸጋሪ ነው። እንደሠለጠነው ዓለም መንግሥት በፖለቲካ ፓርቲ ድጋፍ የሚቋቋምና የሚመራ ቢሆን ኖሮ፤ አሸናፊው ሥልጣን ሲይዝ፤ ተሸናፊው የተቃዋሚ ቦታውን ይዞ ትግሉን መቀጠል ይችላል። በአገራችን ግን ይህን የመሰለው አሠራር የለም። ንጉሠ ነገሥት ሲወድ ይሾማል፤ ወይም ይሽልማል። ሲጠላ ደግሞ ይሽራል ወይም ግዞት ይልካል። የእኔ ጥረት ጸሐፊ ትዕዛዝን ከችግር ለማዳን ያቀረብኩላቸውን መፍትሔ ተቀብለው እንዲፈጽሙና ከጃንሆይ ጋር ግንኙነታቸው እንዲታደስ ነበር። እሳቸው ግን ስላልታያቸው ሐሳቤን አልተቀበሉትም። በዚያን ጊዜ የሚያሳዩትን ሁኔታ ከቀጠሉበት፤ አባ ጠቅል ኃይለሥላሴ እጅግ ቢያንስ ከሽረት እንደማይምሯቸው እርግጠኛ ነበርኩ። በመጨረሻ የደረሰውም ያው የፈራሁት ነው .... " በማለት፤ ጄኔራል መኰንን የሚያውቁትን ገልጠውልኛል።

የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ እንደተናገሩት፤ የጃንሆይና የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ግንኙነት፤ ከአውሮፓ ጉዞ መልስ ጀምሮ ከቀን ወደቀን እየሻከረ መሄዱን በመመልከት፤ "መጨረሻው አያምርም" እያሉ ሥጋት ያደረባቸው ሚኒስትሮች ብዙዎች ነበሩ። የዚህ መጽሐፍ ደራሲ በዚያን ጊዜ በነበረው የጋዜጠኝነት ሥራው "አምሳለ ገነት" አጠገብ ባለው መናፈሻ ሥፍራ ላይ ሚኒስትሮች እየተሰበሰቡ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ የሚወያዩትን የማዳመጥ ዕድል አጋጥሞታል። "ጉዱ በለየለት" እያሉ የሚፎክሩትንና "ሠላም ያምጣልን" በማለት መልካም ስሜታቸውን የሚገልጹትን ሰዎች በትክክል ያስታውሳል።

# ምዕራፍ ፰

# በወልደጊዮርጊስ ጉዳይ የግርማዊት ቪላ ስብሰባ እና ውሳኔ

በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ላይ ንጉሠ ነገሥቱ ስለሚወስዱት እርምጃ፤ የምሥጢር ስብሰባ ይደረግ የነበረው በግርማዊት እቴጌ ቪላ ሐምሌ 19 በተባለው መናፈሻ የአትክልት ቦታ ላይ ነበር። ስብሰባውን ጃንሆይ በቤተመንግሥታቸው ውስጥ ቢያደርጉት የእልፍኝ አሽከሮቹ ሁሉ ስለሚያዩ፤ ምሥጢርነቱን ለመጠበቅ የሚያስተማምን መሆን አይችልም። ስለዚህ፤ ስብሰባው በግርማዊት ቪላ ውስጥ ቢደረግ የተሻለ ይሆናል ተብሎ ታሰበ። በስብሰባው ላይ ተካፋይ የሚሆኑትም ታላላቅ ሰዎች፤ ብዙ ጊዜ ጤና የሌላቸውን ግርማዊትን ለመጠየቅ እንደሚመጡ ለማስመሰል ይመቻል፤ የሚል ሐሳብ ተጨምሮበት ነበር። በዚህ መሠረት፤ ከጃንሆይና ከእቴጌ በስተቀር ልዑል ራስ ካሣ፣ ልዑል አልጋወራሽ፣ ልዑል መኰንን፣ ብፁዕ አቡነ ባስልዮስ፣ አቶ መኰንን ሀብተወልድ የገንዘብ ሚኒስትር እና ደጃዝማች መስፍን ስለሺ የከፋ ጠቅላይ ገዥ የጉባኤው ተካፋዮች እንዲሆኑ ተመረጡ። አቶ መኰንን እና ደጃዝማች መስፍን፤ ሰው እንዳይለያቸው ግርማዊት ቪላ የሚመጡት፤ በአንዲት አልባሌ በሆነች የግራና የቀኝ መስታወቶቿ በጨርቅ በተሸፈነች አውቶሞቢል ነበር። ሌሎቹ ታላላቆቹ መሣፍንትና ብፁዕ አቡነ ባስልዮስ፤ ያው ለወትሮው ግርማዊትን ለመጠየቅ የሚመጡ በመሆናቸው፤ የሚያስጠረጥር ሆኖ አልተገመተም። የዚህ ዓይነቱ ስብሰባ መደረግ ማንም ማወቅ የሌለበትና በከፍተኛ ምሥጢር እንዲጠበቅ መወሰኑን፤ ለግርማዊት እቴጌ ሹማምንቶች፤ ለአዛዥ ተረፈ ወልደገብርኤል ዋና የእልፍኝ አስከልካይ፣ ለበጅሮንድ ገዛኸኝ ገብረማርያም የግርማዊት ዋና ግምጃ ቤት ሹም፣ ለአቶ መንግሥቱ ወልደየስ የግርማዊት ምክትል የእልፍኝ አስከልካይ ተነገራቸው። የመጨረሻው ዋናው ስብሰባ የተደረገው፤ ቅዳሜ ሚያዝያ 1 ቀን 1947 ዓ.ም የሆሣዕና ዋዜማ ዕለት ነበር። ጃንሆይ ስብሰባውን ሲከፍቱ የሚከተለውን መግለጫ ሰጡ።*

" .... ሁላችሁም እንደተረዳችሁት፤ ይኸንን የተለየ ስብሰባ ያደረግነው፤ ለብዙ ዓመታት በታማኝነትና በትጋት ሲያገለግለን የኖረው ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ በማይታወቅ ምክንያት ባሕርዩን ለውጦ፤ በሥራውም ላይ የነበረውን ትጋትና ቅንነት ችላ ብሎታል። ከዚህ በቀር ደግሞ፤ በሥራው ከእኛ ጋር የነበረውን ቅርበት በራሱ ፈቃድ አቋርጦ መራቅን መርጧል። ምን የደረሰብህ ነገር አለ? ብለን ብንጠይቀውም፤ ሥራዬን እሠራለሁ። ድሮም ቢሆን ሳልጠራ መጥቼ አላውቅም፤ የሚል <u>የዕብሪት መልስ እስከ መስጠት ደርሷል</u>። ሁላችሁም እንደምታውቁት፤ አንድ ከፍተኛ የሆነ ኃላፊነትን የተቀበለ ሰው፤ የተመደበበትን ሥራ በመሰላቸት ወይም በአንድ ምክንያት በመቀየም ችላ ማለት ከጀመረ፤ ጉዳቱ የመንግሥታችን መሆኑ ግልጽ ነው። ስለዚህ፤ እሱ ሳይደሰት ሥራውም ስለሚበደል፤ በዚሁ አኳኋን ጉዳዩንም ዝም ብሎ ማቆየት ተገቢ ስላልሆነ፤ የኃላፊነት ለውጥ ለማድረግ በእኛ በኩል ቆርጠናል። ነገር ግን፤ ሰዎች ነንና ተሳስተን ያልተገባ ውሳኔ

---

* ከበጅሮንድ ገዛኸኝ ገብረማርያም የተገኘ

እንዳናደርግ፤ በቅድሚያ የናንተን የታላላቆቹን አስተያየት ለማድመጥ ፈቃዳችን ስለሆነ፤ የምታውቁትንም ሆነ የሚሰማችሁን መናገር ትችላላችሁ .... "

ንጉሠ ነገሥቱ ስብሰባውን በዚህ መግለጫ ከከፈቱ በኋላ፤ የመጀመሪያው አስተያየት ሰጭ የሆኑት የታወቁት መስፍን ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፤ ዓይናቸውን አቶ መኰንን ሀብተወልድ ላይ አተኩረው መናገር ሲጀምሩ፤ የስብሰባው ተካፋይ የሆኑት ሁሉ ምን ይሉ ይሆን? በማለት በከፍተኛ ጉጉት ሲጠባበቁ ይታይ ነበር። በዚያን ሰዓት በአካባቢው የነበሩት በጅሮንድ ገዛኸኝ ገብረማርያም፤ ለብዙ ዘመናት በአእምሮአቸው ተቀርፆ የኖረውን የራስ ካሣን ንግግር የሚያስታውሱት እንደሚከተለው ነበር።

## የራስ ካሣ ንግግር

" .... ባለፈው ጊዜ ቀኑ መቼ እንደነበረ ባይታወሰኝም፤ ስለ ጽሕፈት ሚኒስትሩ ጉዳይ ተሰብስበን ስንወያይ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ በጠበቀ ወዳጅነት ተሳስረው፤ በሥልጣናቸው የፈለጉትን እንደሚያደርጉና፤ ለእኛም ለመሳፍንቶቹ ቅን ሐሳብ እንደሌላቸው፤ ከተመቻቸውም እኛን ከማጥቃት እንደማይመለሱ፤ ብዙዎቹ አምርረው ተናግረው ነበር። አሁን ደግሞ እንደምናየው ከሆነ፤ ነገር ተለውጦ ቀርቦልናል። ሁለቱ በአንድነት ተሳስረው በአንድነት የሚፈልጉትን ሲያደርጉ የኖሩት ሰዎች ተለያይተው፤ መኰንን ሀብተወልድ የእኛ ወገን ሆኖ፤ ያ በአስቸጋሪነቱ የቀጠለውን ወልደጊዮርጊስን፤ ጃንሆይ በምን አኳኋን ከሱ መገላገል እንደሚችሉ መካሪም አማካሪም ሆኖ በመገኘቱ፤ ፈጣሪ ይመስገን ማለት የተገባ ይሆናል። ስለዚህ፤ እንደእኔ! እንደእኔ! ከሆነ ወልደጊዮርጊስ በድንገት ተነሥቶ ይህን ሁሉ የምንሰማውን የዕብሪት ሥራ ከየት እንዳመጣውና በልቡ ቋጥሮ ያስቀመጠው ምኞት የት ለመድረስ እንደሆነ፤ አብሮት ከኖረው ከወዳጁ ከመኰንን ሀብተወልድ የተሻለ የሚያውቅ ስለሌለ፤ እሱ የሚለንን ለማዳመጥ ቅድሚያ ቢሰጠው፤ የተገባ ይሆናል .... "

በራስ ካሣ አነጋገር የገንዘብ ሚኒስትሩ መጠቃታቸውን በማየት፤ ጃንሆይ፤ አቶ መኰንን መልስ ልስጥ ብለው ሳይጠይቁ፤ መኰንን! የምታስበውን ተናገር ብለው ፈቀዱላቸው።

## የመኰንን ሀብተወልድ ንግግር

" .... ልዑል ጌታዬ የተናገሩትን ከፍ ባለ አክብሮትና ከፍ ባለ ጥንቃቄ አድምጫለሁ። ልዑልነትዎ እንዳሉት፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ እና እኔ በወዳጅነት ብቻ ሳይሆን እንደ ወንድማማች የምንተሳሰብ ነበርን። ይህም አንድነታችንና ቅርበታችን፤ በምንወዳቸው ጌታችን በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መሪነት የኢትዮጵያን ሕዝብ ለማገልገል እንጂ፤ በግል ጥቅም ላይ የተመሠረተ አለመሆኑን ስመ እግዚአብሔር ጠርቼ መናገር እችላለሁ። እርግጥ ዛሬ፤ እኔና ጸሐፊ ትዕዛዝ በመካከላችን አለመግባባት ተፈጥሮ፤ እንደድሮአችን መሆን አልቻልንም። ልዑልነትዎ እንደሚያውቀው፤ ይህም ዓይነቱ ሁኔታ በሰው ልጆች ላይ የሚደርስ በመሆኑ፤ እኛ የመጀመሪያዎቹም የመጨረሻዎቹም አይደለንም። እውነተኛውና ትክክለኛው ምክንያት ምን

እንደሆነ ባይገለጥልኝም፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በብዙ ሁኔታ መለወጡን አውቃለሁ። ጃንሆይም ቢቸግራቸው ጠርተው፤ የደረሰብህ ነገር አለ ወይ? ብለው ቢጠይቁት፤ ምን መልስ እንደሰጣቸው ነግረውናል። በሌላም በሥራ ጉዳይ ጓደኞቻችን ሚኒስትሮች እንዳስተዋሉት፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በአኳኋኑም ሆነ በአነጋገሩ ከድሮው ሁኔታ በጣም መለወጡ በግልጽ ይታያል። በዚህም ምክንያት፤ አንዳንድ ሰዎች ጸሐፊ ትዕዛዝ ይህን ሁሉ የመለወጥ ሁኔታ የሚያሳዩት፤ ቤተመንግሥትም ካልተጠራሁ አልመጣም እስከማለት የደረሱት፤ አንድ የሆነ ኃይል አዘጋጅተው መንግሥት ለመገልበጥ ቢያስቡ አይደለም ወይ? በማለት ብዙ የሚያወሩና የሚጨነቁ አሉ። በእኔ በኩል ጸሐፊ ትዕዛዝን ደህና አድርጌ አውቀዋለሁ። ስለማውቀውም በአንዳንድ በሌሎች አገሮች እንደሚደርሰው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በጃንሆይ መንግሥት ላይ ለመሸፈት ያስባል ወይም ይመኛል ብዬ አላስብም። ጸሐፊ ትዕዛዝ ለንጉሠ ነገሥታችን ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ያለውን ታማኝነት መካድ አይቻልም። ልዑል ጌታዬ ራስ ካሣ ቅድም ሲናገሩ፤ የጸሐፊ ትዕዛዝ ሐሳቡና ዓላማው ምን እንደሆነ ከመኰንን ሀብተወልድ በቀር የሚያውቅ ሌላ ሰው ስለሌለ፤ እሱ ይንገረን ብለዋል። ስለዚህም፤ የማውቀውን ይኸው ተናግሬአለሁ። ይሁን እንጂ፤ ሰዎች የተጨነቁበትንና የተወራን ወሬ ዝም ብሎ ማየትና ማቃለል የተገባ ስላልሆነ፤ አንዳንድ ክትትል ቢደረግ፤ የሚያስፈልግ ይመስለኛል። ለዚህም ኃላፊ የሆኑ ሰዎች እንዲመደቡ ያስፈልጋል …. "

ጃንሆይ የአቶ መኰንን ሀብተወልድን ንግግር ካደመጡ በኋላ፤ ራስ ካሣን አሁን ደግሞ ምን ታስባለህ? ብለው ጠየቋቸው።

<u>ራስ ካሣ</u>

በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ፤ እኔ ከዚህ ቀደም የማስበውን ሁሉ ተናግሬአለሁ። ባለፈው ጊዜ ጃንሆይ ሰብስበውን ስለ ሰውየው ባሕሪ መለወጥ በብዙ ተመካክረንበት የተወሰነ ነገር አለ። ይኸውም፤ ጃንሆይ ከዚያ ከረዥሙ ጉዞዎ ከአሜሪካና ከእንግሊዝ ሲመለሱ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝዎን እንዲለውጡ ሁላችንም የተስማማንበት ጉዳይ ነው። <u>"ጸሐፊ ትዕዛዝዎን ይለውጡ"</u> ሲባል፤ በዚያ በመከራው ዘመን ያልተለየዎትን አገልጋይዎን፤ ይሡሩት፤ ወይም ወደ ግዞት ይላኩት ማለት አይደለም። ከአሁኑ ሥራው ወደሌላ ቀለል ወደአለ ሥራ ያዛውሩት ነው።

<u>ጃንሆይ፤</u>

አየህ ራስ ካሣ፤ ምናልባት ዘንግተኸው ይሆናል። ይኸን ጉዳይ ባለፈው ስብሰባችን ስንነጋገር፤ ስለ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ ከጠቅላላ ስምምነት ላይ ደረስን እንጂ፤ ቁርጥ ውሳኔ አልሰጠነውም ነበር።

<u>ራስ ካሣ፤</u>

እንግዲያውማ ማለፊያ ነው። በእኔ በኩል በዚያን ጊዜ የተናገርኩት ዛሬም ስላልተለወጠ፤ ቁርጥ ውሳኔ እንዲደረግበት አሳስባለሁ። …. ሆኖም ጊዜ እንዳይፈጅ መታሰብ አለበት። …. አሁን አቶ መኰንን ሀብተወልድ ሲናገር፤ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር በአንድነት የሠራነው ሁሉ ለአገር ጥቅም እንጂ ጥፋት አይገኝበትም ብሏል። አሁን ማን ይሙት? እናንተ በእኛ ላይ



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ በግል ሲጫዋወቱ፤

ትዶልቱብን የነበረውን ገልጣችሁ ትነግሩናላችሁ? ግዴላችሁም! እኛም ከእናንተ አንጠብቅም። አሁን ወደ ቀድሞው ታሪክም ተመልሶ መነጋገር አያስፈልግም። ዛሬ ሁሉም አልፎ ወደ ሌላ ጠባይና አሠራር መሸጋገሪያ ላይ ስለምንገኝ፤ የወደፊቱን ተስፋችንን እግዚአብሔር ያቃናልን።

<u>አቡነ ባስልዮስ</u>

ጸሐፌ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ሁላችንም እናውቀዋለን። ይኸውም፤

አንደኛ/ ለጃንሆይ ታማኝነቱንና በቅን ማገልገሉን ነው። በተለይም በዚያ በመከራው ዘመን አንድም ቀን ከጌታው ሳይለይ ጨዋነቱን ያስመሰከረ መሆኑን ነው።

ሁለተኛ/ ጃንሆይም፤ ከጽሕፈት ሥራ አንሥተው በየጊዜው እያሳደጉ፤ እስከ ትላቁ ሹመት ጸሐፊ ትዕዛዝነትና ሚኒስትርነት አድርሰውታል። በሹመቱ፣ በዕድገቱ፣ በሽልማቱ ምንም የተጓደለበት ነገር እንደሌለ ሁላችንም እናውቃለን። እሱም ደህና አድርጎ ያውቃል። አሁን በቅርቡ አንዳንድ የምመለከተው ነገር ከወትሮው የተለየ ስለሆነብኝ፤ ጃንሆይም በዚህ ሰው ጉዳይ ምን ያህል እንዳሰቡበት ስለገለጹልኝ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ጠርቼ፤ ምነው እንደድሮህ አላይህም? ከጌቶቹ ጋር የደረሰ ነገር አለ ወይ? ብዬ ብጠይቀው፤ መጀመሪያ ምንም የማውቀው ነገር የለም ካለኝ በኋላ ወዲያው ቀጠለና፤ " .... አንድ ቀን ጃንሆይ ጠርተው ልብህም እግርህም ከእኛ የራቀ መስሎናል ምክንያቱ ምንድን ነው? ብለው ቢጠይቁኝ፤ ቀድሞውንም ቢሆን ጃንሆይ ሳይጠሩኝ መጥቼ የማላውቅና በቢሮዬም ሥራዬን ከመሥራት እንዳልቦዘንኩ ነገርኳቸው .... በውጭ ግን ጠላቶቼ ያውም ወዳጆቼ የነበሩት ሁሉ፤ እነ ..... ብሎ ስም ከዘረዘረ በኋላ፤ የሚሠሩብኝን ክፋት አስረድቼ፤ ጃንሆይ የሰው ነገር ሰምተው ይጥሉኛል ብዬ እንደማልጨነቅ ነግሬአቸዋለሁ አለኝ። እኔም ምክሬን ሰጠሁት። ጃንሆይ እኮ የጠየቁህ ትልቅ ቁም ነገር ነው። እሳቸው አስበው፤ ምነው? ልብህም እግርህም ራቀን ብለው ሲጠይቁህ፤ መልስህ ልክ አይደለም። ልጅ ለአባቱ የሚሰጠው መልስ አይደለም። አሁንም አንተው ራስህ ሄደህ፤ ጫማቸው ላይ ወድቀህ ያጠፋሁት እንዳለ ይማሩኝ፤ የማሻሽለው እንዳለ ይምከሩኝ፤ ብለህ፤ እውነተኛ ሐሳብህን ግለጥላቸው። <u>እንደ ልጅ አሳድገውሃል፣ እንደ አዋቂ አሸምግለውሃል፣ በትልቁ ሾመውሃል፣ ዕምነታቸውን ጥለው እንደልብህ እንድትሠራ ዕድሉን ሰጥተውሃል። ከዚህ የበለጠ ምን ያስፈልግሃል</u>? .... ብዬ መከርኩት። አሁን እንደሰማነው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ የሚጠበቅበትን አላደረገም። እኔም የመከርኩትን አልፈጸመም። በዚህስ ሁኔታው የሚቀጥለው እስከ መቼ ድረስ ነው? .... ጃንሆይ የሚያስቡትን ሁሉንም ገልጸውልናል። እሱ ስላልተደሰተ፤ ሥራው መበደል የለበትም። በዚህም ምክንያት ልዑል ራስ ካሣ ደህና አድርገው እንዳሳሰቡት፤ ጃንሆይ ጸሐፊ ትዕዛዝን ወደ ሌላ ሥራ ቢያዛውሩት ተጐዳ፤ ተቀጣ፤ የሚያሰኝ አይደለም። ጃንሆይ አልጨከኑበትም .... "

ጃንሆይ፣

" .... አሁን አባታችን የነገሩን እውነተኛውንና ትክክለኛውን ጉዳይ ነው። እኔም የዚህ ሰው ሁኔታ ወደ ጠብ የሚገፋፋኝ ስለመሰለኝ፣ አባታችን በጸሎት ያስቡን ብዬ ነግሬዎት ነበር። እርስዎም ራስዎ፣ የወልደጊዮርጊስን መለወጥ ከተገነዘቡ በኋላ፣ ጠርተው ምን ደርሶብሃል? ብለው እስከመጠየቅ የደረሱት፣ ወደ ቀና መንገድ እንዲያመራ በማሰብ ነበር። ነገር ግን እሱ አልፈለገም። እርስዎ አነጋግረው ከመከሩትም በኋላ፣ ወደ እኛ መጥቶ የደረሰበትን ለመናገርና ይቅርታም ለመጠየቅ ፈቃደኛ አልሆነም።

.... ሁላችሁም እንደምታውቁት እኛ ስለ ወልደጊዮርጊስ ያለን ግምት ትልቅ ነበር። እስከ ዛሬ ድረስ በአገልግሎቱ በመደሰትና በችሎታውም በመተማመን፣ እንደ እሱ ያቀረብነው ሌላ ሰው አልነበረም። እስከዚህም በትዕግሥት ስናስታምመው የቆየነው፣ ላደረገልን አገልግሎት ከፍተኛ ግምት በመስጠት ነው። አሁን ግን በቅቷል። ከዚህ የበለጠ ማስታመም አያስፈልግም። ብዙ ዓመታት በመቆየት፣ ከተሰላቸበትና ቅሬታ ካደረበት ሥራው፣ ወደ ሌላ ቦታ እንዲዛወር ተቆርጧል። ራስ ካሣ እንዳልከው፣ አባታችንም እንደተናገሩት፣ የሥራ ዝውውሩን በደንቡ መሠረት ከተቀበለ፣ ምንም የሚደርስበት ነገር የለም። ነገር ግን፣ አልቀበልም ብሎ ካንገራገረ፣ ይታሠራል።

ራስ ካሣ፣

ይፈቀድልኝና እኔ አንድ ሐሳብ አለኝ። የንጉሥ ትዕዛዝ አልቀበልም ብሎ ካስቸገረና እንዲታሠር አስፈላጊ ከሆነ፣ እኔ ዘንድ ተይዞ ሊቆይ ይችላል።

ጃንሆይ
ከረር ባለ ቃል

እኛ እኮ፣ ለወልደጊዮርጊስ ካንተ ያነሰ አናስብለትም። እንዲጉዳም አንፈልግም። ማሠር ካስፈለገንም፣ እንደ ማንም እሥረኛ አንቆጥረውም። እዚህ ደረጃ እንዳይደርስ የተቻለንን ሁሉ እናደርጋለን። ሳንወድ በግዴታ ማሠር ካስፈለገን፣ ማንኛውንም ነገር ተሟልቶ ደህና ማረፊያ እንዲሰጠው ስለምናደርግ፣ አንተ ቤት መሄድ የለበትም። አንተ የጠየቅከው ይፈጸም ቢባል፣ በውጭ አገር ጋዜጦች ላይ የሚደርስንን ወቀሳ ማሰብ ያስፈልጋል። ንጉሠ ነገሥቱ ያስቸገረውን ሚኒስትር እንዲያስርለት ለወንድሙ ሰጠው ተብሎ እንዲወራ አንፈቅድም።

አቡነ ባስልዮስ፣

መቸም፣ ለክፉም ለደጉም ማንኛውንም ነገር ቀደም አድርጉ ማሰቡ የተገባ ነው። ቢሆንም እስከ እሥራት የሚያደርስ ነገር ጃንሆይን ይገጥማቸዋል ብዬ አላስብም። ጃንሆይ ደህና አድርገው ነግረውናል። በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ላይ የሚወስኑት፣ አባት ልጁን እንደሚቀጣ ያህል ነው እንጂ፣ ከዚያ በላይ እንዳልሆነ ሁላችንም ማመን አለብን።

ጃንሆይ፤

አባታችን እንዳሉት፤ እኛም ወልደጊዮርጊስን እንደምናውቀው፤ ትዕዛዛችንን አሻፈረኝ እስከ ማለት ይደፍራል ብለን አናስብም። ሆኖም በሰው አዕምሮ ላይ የሚፈጠረውን ሐሳብ መተንበይ ስለማይቻል፤ ጥንቃቄውን እንደ ሁኔታው ማዘጋጀት የተገባ ነው። እዚህ ላይ፤ ቅድም መኰንን ሀብተወልድ የተናገረውን ችላ ብለን ልናልፈው አይገባም። በመኰንን አስተያየት፤ ወልደጊዮርጊስ በመንግሥታችን ላይ ለመሸፈት ሐሳብም ምኞትም እንደሌለው አረጋግጣለሁ ብሏል። ቢሆንም፤ ብዙ ሰዎች የተጨነቁበትንና የሚነዛውን ወሬ ማቃለል የተገባ ስላልሆነ፤ መከታተል ማስፈለጉን ተናግሯል። ለዚህ ጉዳይ፤ መኰንን ሀብተወልድ ከክብር ዘበኛ አዛዦችን ጋር ሆነህ፤ በጦር ወታደሮችና በፖሊስ ሠራዊት በኩል፤ መስፍን ስለሺ፤ በአርበኞችና በስደተኞች ሠፈር፤ ስለ ወልደጊዮርጊስ ምን እንደሚታሰብ፤ ይኸ ደጋፊዎቹን በያለበት በተለይም በጦሩ ክፍል አዘጋጅቷል እየተባለ የሚወራው ወሬ እውነቱ እስከ ምን ድረስ እንደሆነ ተከታትላችሁ፤ የደረሳችሁበትን በቶሎ አስታውቁን።

ራስ ካሣ፤

ጃንሆይ! መቸም እነዚህ ሁለት ሰዎች የጽሕፈቱም የገንዘቡም ባለሥልጣኖች፤ አብረው ብዙ ጉዳዮች የሠሩና በጣም የሚተዋወቁ በመሆናቸው፤ ቀደም ብዬ እንደተናገርኩት ስለ ወልደጊዮርጊስ ከመኰንን ሀብተወልድ የተሻለ የሚነግረን ስለሌለ፤ እሱ የሚለውን በዕምነት መቀበሉ የተገባ ነው።

ጃንሆይ፤

አየህ ራስ ካሣ! አንተ የምታስበውንና የሚመስልህን ሁሉ አውጥተህ በግልጽ መናገርህን የሚጠላ የለም። ሕይወትህን ሙሉ ለምታምንበት ስትታገል የኖርክ መሆንህን ያልተረዳ የለም። ሁሉም ያውቅልሀል። ነገር ግን፤ በዚህ በመኰንን ሀብተወልድና በወልደጊዮርጊስ ወዳጅነትና ተደጋግፎ መሥራት እስከ ዛሬ ድረስ የጠቀመው፤ እኛንና መንግሥታችንን መሆኑን ስንናገር ሳይገርምህ አይቀርም። ሐቁ ግን ይኸ ነው። ይህም እውነት መሆኑን አንተው ራስህ መርምረህ እንድትረዳው በሚያመች ጊዜ ማስረጃዎቹ እንዲቀርቡልህ እናደርጋለን።

ራስ ካሣ፤

መቸም ንጉሠ ነገሥት ባለው ትልቅ ኃላፊነት ራሱ መርምሮና ተረድቶ የሚወስነው አለ። ሌላ ጊዜም በመካሪዎቹ እየተጠቀመ የሚሠራው አለ። የድሮዎቹ አበዎች ሲናገሩ፤ ቤተመንግሥት ያለ መካር፤ ቤተክህነት ያለ መምህር አይሆንም ይላሉ። በእኔ በኩል የወልደጊዮርጊስና የመኰንን ሀብተወልድ ፍቅር የተገነባው፤ በምን ላይ እንደሆነ የማውቀውን አውቃለሁ። የተለየም ማስረጃ እንዲሰጠኝ ጃንሆይን አላስቸግርም። አሁን እኮ ጉዳዩ አልቆ የሁለቱም ሰዎች ፍቅር አክትሞ፤ ወደ ሌላ ጉዳይ አምርተናል። ጃንሆይ እንዳሉት፤ በዛሬው ስብሰባችን ዋና ጉዳይ አድርገን

የምንነጋገርበት፤ ስለ ወልደጊዮርጊስ ብቻ ነው። እሱንም ሁላችንም የተስማማንበትን ለጃንሆይ ገልጸናል። ሌላ የሚጨመር የለም።

## የስብሰባው ፍጻሜ

## አጅሬ እንዲሻሩ ሁሉም ተባበሩ

## አቡኑም አልቀሩ!

ከዚህ በላይ እንደታየው፤ በኢትዮጵያ ሥርዓት በታወቀው የዓቢይ ጾም ውስጥ በሆሣዕና በዓል ዋዜማ፤ ቅዳሜ ሚያዝያ 1 ቀን 1947 ዓ.ም፤ ከእኩለ ቀን በኋላ በዐሥር ሰዓት፤ በግርማዊት እቴጌ ቪላ በከፍተኛ ምሥጢር በተደረገው ጉባኤ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ ከጽሕፈትና ከፍርድ ሚኒስትርነታቸው ተነሥተው ወደ ሌላ ሥራ እንዲዛወሩ ሁሉም ተስማምተው ተለያዩ።

በወልደጊዮርጊስ ላይ የተወሰነው ይህ የሥራ "ዝውውር" የተባለው ቃል፤ ውስጠ ምሥጢሩ "ሽረት" መሆኑን ለመረዳት የሚቸገር የለም። ጃንሆይ ባደረጉት ስብሰባ ላይ የተካፈሉት፤ ግርማዊት እቴጌ መነን፣ ልዑል አልጋወራሽ፣ ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፣ ልዑል መኰንን ኃይለሥላሴ፣ ብፁዕ አቡነ ባስልዮስ፣ አቶ መኰንን ሀብተወልድና ደጃዝማች መስፍን ስለሺ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ አስተያየታቸውን ሲሰጡ፤ ምንም እንኳ የሥራ ዝውውሩን አስፈላጊነት ያለ ማመንታት ቢቀበሉትም፤ ሰውየው በኢትዮጵያ ነፃነት ላይ በደረሰው የመከራ ዘመንና ኋላም በሰላሙ ጊዜ ለንጉሠ ነገሥቱና ለአገራቸው ያበረከቱትን አገልግሎት፤ በሚገባ የተገነዘቡ መሆናቸውን፤ ሁሉም በአንድ ቃል ተናግረዋል። በመንግሥት የፖለቲካ ጉዳይ ላይ የማይካፈሉት ግርማዊት እቴጌ እንኳ፤ ከዚህ በፊት በተደረገው የንጉሣዊው ቤተሰብ ስብሰባ ላይ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሲናገሩ፤ " ..... በዚያ በመከራው ዘመን ይኽ ሰው ጃንሆይን ሳይለይ፤ እስከ ደስታችን ቀን ድረስ ያገለገለ ስለሆነ፤ አሁን ካለበት ሥራ የሚዛወረው ጉዳት እንዲያገኘው ሳይሆን፤ ሥልጣኑ ብቻ እንዲቀነስ ነው። ስለዚህ፤ ከቀለቡም፣ ከመሰቡም መጓደል የለበትም ..... " ብለዋል።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በመጨረሻ ለጉባኤው ባሰሙት ንግግር፤ ሁላችሁም የገለጻችሁት አስተያየት ተመሳሳይና ከሐሳባችን ጋር የሚገጣጠም ስለሆነ ደስ ብሎናል ካሉ በኋላ፤ " .... በእኛ በኩል የተቀረጠው ውሳኔ ከትንሣኤው በዓል በኋላ እንዲፈጸም ይደረጋል። እስከዚያው ድረስ ግን፤ ዛሬ ተነጋግረንበት የተወሰነው ጉዳይ፤ በጥብቅ ምሥጢር ተጠብቆ እንዲቆይ ይሁን ... " በሚል ቃል ስብሰባውን ዘጉ።

# ምዕራፍ ፱

## የወልደጊዮርጊስ የመጨረሻይቱ ቀን

**ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም**

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር፤ ሰኞ ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም ጠዋት ወደ ቢሮአቸው ሲያመሩ፤ ይህች ቀን እንደሌሎቹ ቀናት ውላ የምትመሽ እንጂ፤ የእሳቸው ሹመትና የወደፊት የሥራ ዓለም የሚወሰንባት ቀን እንደምትሆን አያውቁም ነበር።

በሕማማቱ መግቢያ ከሰኞ ሚያዝያ 3 ቀን 1947 ዓ.ም ጀምሮ ጤና አጥተው ስለሰነበቱ፤ ለትንሣኤው በዓል ሚያዝያ 8 ቀን ሌሊት፤ እንደልማዳቸው ቤተክርስቲያን እንኳ መሄድ አልቻሉም ነበር። በበዓሉ ዕለት ወደ ማታ በኮሎኔል መኰንን ደነቀ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ በኩል፤ ጃንሆይን በስልክ አስፈቅደው፤ ለጥቂት ቀናት ዕረፍት ለማድረግ ቢሾፍቱ ከሚገኘው ከገጠር ማረፊያ ቤታቸው ሄዱ። አንድ ሳምንት ያህል በቢሾፍቱ በሰነበቱበት ሰሞን ጤናቸው ስለተሻሻለ፤ የዳግማዊ ትንሣኤ ማግሥት ሰኞ ሚያዝያ 17 ቀን በማለዳ ተነሥተው፤ ከጠዋቱ በሦስት ሰዓት እንደ ተለመደው እቢሮአቸው ለመገኘት ወሰኑ። ይሁን እንጂ፤ በዚህ ዕለት እሳቸው የጽሕፈት ሚኒስቴር ጽሕፈት ቤታቸውን ሲያስቡ፤ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ግቢ ውስጥ ተዘጋጅቶ የሚጠብቃቸው ድግስ ሌላ ነበር።

ገና ከቢሾፍቱ ወደ አዲስ አበባ ጉዞ ሳይጀምሩ፤ እሑድ ሚያዝያ 16 ቀን የዳግማዊ ትንሣኤ ዕለት፤ አባ ሐና ጅማ የጃንሆይ ልዩ አሽከርና ዋና የግምጃ ቤት ኃላፊ፤ ቢሾፍቱ ከሚገኘው* "ፌርፌልድ" ከተባለው የጃንሆይ ማረፊያ ቤት በስልክ ደውለው፤ በዚያ ያገኙትን ጠባቂውን ዘበኛ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ደህንነት ጠይቅና ንገረኝ! ብለው ላኩት። የፌርፌልድ ጠባቂ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ቤት ሄዶ የአባ ሐናን መልዕክት ሲያደርስላቸው፤ ሕመማቸው መሻሻሉንና ነገ ሰኞ ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም በማለዳ ተነሥተው፤ ወደ አዲስ አበባ ለመምጣት መዘጋጀታቸውን ነገሩት። "የፌርፌልድ" ጠባቂ ይህን መልካም ዜና ለአባቴ ሐና በስልክ ካበሠረ በኋላ፤ እሳቸው ደግሞ ወዲያውኑ ለጃንሆይና፤ የወልደጊዮርጊስን የሚያዝያ 17 ቀን የሽረት በዓል ለሚያዘጋጁት ዋና ዋና ሰዎች እንዲያውቁት አደረጉ። ይህ ሁሉ ሲሆን፤ አዲስ አበባ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ተደግሶ የሚጠብቃቸውን አጀሬ እንዴት በቅድሚያ ሳይደርሱበት ቀሩ? ....

ቀደም ሲል የዘውድ ምክር ቤትና ንጉሣውያን ቤተሰብ አልፎ አልፎ በግርማዊት ቪላ እየተሰበሰቡ፤ ስለ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ ውይይት ማድረጋቸውን ጸሐፊ ትዕዛዝ ቢደርሱበትም፤ በመጨረሻው ሚያዝያ 1 ቀን ቅዳሜ የተካሄደውን

---

* "ፌርፌልድ" ጃንሆይ እንግሊዝ አገር በስደት ያሳለፉበት ቤት ነው። ይህንኑ ቤት የሚመስል ቢሾፍቱ አሠርተው ማረፊያቸው አድርገውት ነበር።

ስብሰባና የተደረገውን ውሳኔ አልሰሙም ነበር:: ካለፉት አራት ወራት ጀምሮ ወልደጊዮርጊስን እንዲከታተል የተመደበው የፀጥታ ጓድ፤ " .... **ከግርማዊት እቴጌ የእልፍኝ አሽከሮች መካከል የጸሐፊ ትዕዛዝ ልዩ ወዳጅ የሆነ አንድ ሰው፤ በግርማዊት ሺላ በምሥጢር የሚደረገውን ስብሰባ እየተከታተለ በቴሌፎን የሚያቀብል መሆኑን ደርሰንበታል:: ለጊዜው ግን፤ የዚህን ሰው ስሙንና ማንነቱን ማወቅ አልቻልንም** ..... " ሲል ሪፖርቱን ለአገር ግዛት ሚኒስትሩ ለራስ አበበ አረጋይ አቀረበ:: ይህም ልዩ የፀጥታ ጓድ የሚመራው፤ በኰሎኔል (ኋላ ብ.ጄ) ለማ ገብረማርያም ሲሆን፤ በተደረገው ብርቱ ክትትል ከግርማዊት ዋና ዋና ሰዎች መካከል፤ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የቅርብ ወዳጅነታቸው የታወቀው አዛዥ ተረፈ ወልደገብርኤል መሆን አለባቸው ተባለ:: ከሚወራው ወዳጅነት በስተቀር የተለየ ማስረጃ ባይገኝም፤ ከዚህ ዕለት ጀምሮ የግርማዊት ዋና የእልፍኝ አስከልካይ የሆኑት አዛዥ ተረፈ፤ ከቤታቸው አርፈው እንዲቀመጡ፤ ከቤታቸው አጥር ግቢ እንዳይወጡ፤ ከማንም ሰው ጋር (ከቤተሰቦቻቸው በስተቀር) ያላቸውን ግንኙነቶች ሁሉ እንዲያቋርጡ ተወሰነባቸው::

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ቢሾፍቱ በነበሩበት ሰሞን፤ በአዛዥ ተረፈ ወልደገብርኤል ላይ የተወሰደውን እርምጃ አልሰሙም ነበር:: ሚያዝያ 17 ቀን ከጠዋቱ ሦስት ሰዓት ተኩል ላይ ከጽሕፈት ሚኒስቴር ቢሮአቸው፤ አዛዥ ተረፈን በቴሌፎን ለማነጋገር ቢፈልጉ አላገኟቸውም:: የቤታቸውም ስልክ ይጠራል እንጂ አይመልስም:: ኋላ ቢቸግራቸው፤ የግርማዊትን ዋና ግምጃ ቤት ሹም በጅሮንድ ገዛኸኝን በስልክ አግኝተው፤ **ምነው አዛዥ ደህና አይደለም ወይ? የቢሮውም የቤቱም ስልክ አይመልስም ብለው ጠየቋቸው::** በጅሮንድ፤ አዛዥ ተረፈ ከቤታቸው እንዳይወጡ መጋዛቸውን መናገር አልፈለጉም:: "ለሥራ ጉዳይ ወደ አምቦ ቤተመንግሥት ሄዶ ይሆናል" የሚል መልስ ሰጧቸው:: ጸሐፊ ትዕዛዝ በዚህ አልተረኩም:: ወዳጃቸው የሆኑትንና ከአዛዥ ተረፈም ጋር የጋብቻ ዝምድና ያላቸውን ፊታውራሪ ኃይለሚካኤል ዘውዴን በስልክ አግኝተው፤ አዛዥን ፈልጌ አጣሁት:: የት ነው ያለው? ብለው ጠየቋቸው:: ፊታውራሪ የሚያውቁትን ተናገሩ:: **" ምክንያቱን አላወቅነውም:: ወንድማችን አዛዥ ከቤትህ እንዳትወጣ፤ ከማንም ሰው ጋር ግንኙነት እንዳታደርግ ተብሎ ተወስኖበታል"** አሏቸው:: ጸሐፊ ትዕዛዝ አዘኑ:: ምናልባት በእኔ ምክንያት ይሆን? የሚል ጥርጣሬ አደረባቸው:: ሆኖም ዝም ብሎ ከማዳመጥ በስተቀር ለጊዜው ሌላ የሚያደርጉት አልነበረም::

## የሽረቱ ዝግጅትና አፈጻጸም

1. **ሚያዝያ** 17 **ቀን** 1947 **ዓ.ም ለቶ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከልማዳቸው ውጭ አምሳለ ገነት ከተባለው ጽሕፈት ቤታቸው ሳይሄዱ፤ በገነት ልዑል ቤተመንግሥታቸው "እረንጓዴ ሳሎን" ውስጥ እስከ እኩለ ቀን ስድስት ሰዓት ድረስ ቆዩ::**

2. ከጠዋቱ ሦስት ሰዓት ተኩል ላይ በአረንጓዴው ሳሎን ውስጥ ለሃምሳ ደቂቃዎች ያህል አጭር ስብሰባ አድርገው፤ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ሽረት አፈጻጸም በመጨረሻው የተዘጋጀውን ፕሮግራም አጸደቁ:: በስብሰባው ላይ የተገኙት እንዚያው ከዚህ ቀደም በወልደጊዮርጊስ ጉዳይ ይሰበሰቡ የነበሩት፤ ግርማዊት እቴጌ፣ ልዑል አልጋወራሽ፣ ልዑል ራስ ካሣ፣ ልዑል መኰንን፣ አቡነ ባስልዮስና ደጃዝማች መስፍን ስለሺ ናቸው:: ከስብሰባው ፍጻሜ በኋላ

ሁሉም ወደየጉዳያቸው ሲመለሱ፤ ጃንሆይና አቡነ ባስልዮስ ብቻ በአረንጓዴው ሳሎን እንዲቆዩ ተደረገ።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከጠዋቱ ሦስት ሰዓት ጀምሮ በጽሕፈት ቤታቸው ሲሠሩ ከቆዩ በኋላ አራት ሰዓት ሲሆን፤ ለሁለት ሳምንት ያህል ያላይዋቸውን ንጉሠ ነገሥት እጅ ለመንሣት ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት በደረሱ ጊዜ፤ ጃንሆይ በቆይታ ንግግር ላይ ስላሉ እንዲጠባበቁ ተነገራቸው። ልክ አራት ሰዓት ተኩል ሲሆን፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወደ አረንጓዴው ሳሎን እንዲገቡ ተጠሩ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ጃንሆይን እጅ ሲነሡ፤ እንዴት ሰነበትክ? ብለው ቢሾፍቱ በሰነበቱበት ወቅት ጤናቸው ስለመሻሻሉ ጥቂት ካነጋገሯቸው በኋላ፤ ወልደጊዮርጊስ ያልጠረጠሩትንና ያልጠበቁትን ውሳኔ ከዚህ እንደሚከተለው ገለጹላቸው።

ስማ! ወልደጊዮርጊስ! ብለው ጀመሩ። " ... ዛሬ የጠራንህ፤ ስለ አንተ ጉዳይ የተወሰነውን፤ እኛው ራሳችን በቀጥታ ብንነግርህ የተሻለ ይሆናል ብለን ነው።

- ከዚህ ቀደም ልብህም፣ እግርህም ከእኛ መራቁን አይተን ምን ሆነሃል? ብለን ብንጠይቅህ፤ ጥያቄያችን ሳይከብድህ ስለቀረ፤ የምታስበውን ልትገልጽልን አልፈለግህም።
- ከዚህ ሌላ ደግሞ አንድ ሌላ ጉዳይ አንሥተን ስናነጋግርህ፤ ሎንዶን በምንደርስ ጊዜ እናገራለሁ ብለህ የሰጠኸውን ቃል ሳትፈጽም ቀርተሃል።
- ይህንኑ ጉዳይ ደግመን ብንጠይቅህም፤ "ያንኑ የመንግሥት ሥራ ጉዳይ በስደተኛ ቋንቋ ለማስረዳት ነው እንጂ፤ ጉዳዩ ቢቀርም ፍሬ የለውም ብዬ ትቸው ነው፤ የሚል የተሸፋፈነ ምላሽ ሰጥተኸናል።
- ከዚህ በቀር ደግሞ፤ ሥራህን ችላ ብለኸዋል። ባሕርይህም ተለውጦ አግኝተነዋል።

ስለዚህ፤ ይህ ሁሉ የደረሰው፤ ምናልባት በሥራ ብዛት ሊሆን ይችላል ብለን ብናስብም፣ በሌላ በኩል ደግሞ አንተም ራስህን አሁን ካለህበት ሁኔታ ማረም እንደሚገባህ አይተን፤ ወደ ሌላ ሥራ ልናዛውርህ ወስነናል .... " አሏቸው።

ጸሐፊ ትእዛዝ ምንም እንኳ የተወሰነባቸው የሥራ ዝውውር ምን እንደሆነ ባይገለጥላቸውም፤ የጃንሆይ አነጋገርና አኳኋን ከመቸውም ጊዜ እጅግ የተለየና የከረረ ስለሆነባቸው፤ ትሕትና በተመላበትና በረጋ መንፈስ ከተዘረዘሩት ጥፋቶች ውስጥ፤ ለሁለቱ ጉዳዮች መልስ ለመስጠት ሞከሩ።

አንደኛ/ ልብህም እግርህም ርቆናል ለተባለው ከዚህ ቀደም እንዳሉት ሳልጠራ መጥቼ የማላውቅ በመሆኔ ነው አሉ።

ሁለተኛ/ እንግሊዝ አገር እናገራለሁ ብዬ የነበረው፤ ያንኑ የመንግሥት ሥራ ጉዳይ ስለሆነ፤ መላልሶ መናገሩ ማሰልቸት ይሆናል ብዬ ነው የተውኩት አሉ።

እነዚህን የሁለት ጉዳዮች መልስ ከሰጡ በኋላ፤ ጃንሆይ ይቅርታ አድርገውልኝ የታሰበው ዝውውር እንዲቀርልኝ ሲሉ አመለከቱ። ጃንሆይ ወዲያውኑ በሰጧቸው መልስ፤ " አይቻልም፤ የተወሰነው መፈጸም አለበት" አሏቸው። በዚህ ጊዜ ጸሐፊ ትዕዛዝ አንድ ያልተጠበቀ፤ ኃይለኛ ነው ተብሎ የሚገመት ጥያቄ አቀረቡ። " ... ይኸ በእኔ ላይ የተወሰነው፤ ማንን ደስ ለማሰኘት ነው? ጃንሆይን? ወይስ ሌሎችን? .... " ብለው ጠየቁ። ጃንሆይ የቀረበላቸው ጥያቄ ድፍረት ሆኖ ታያቸው። በቁጣ አነጋገር፤ " ... እኔው ራሴ አመዛዝኜ ያደረግሁት እንጂ፤ ሌላ ሰው ለማስደሰት የማደርገው ነገር የለም። ታውቀኝ የለም እንዴ! .... " የሚል መልስ ሰጧቸው። ወዲያው ጸሐፊ ትዕዛዝ ረገብ ብለው፤ ጃንሆይን ደስ የሚያሰኝ ከሆነ መልካም ነው። እቀበላለሁ ብለው "ለዘለዓለም ያንግሥ" የሚለውን የተለመደ የምኞት ቃል በመጥቀስ እጅ ከነሡ በኋላ፤ ከአረንጓዴው ሳሎን ሲወጡ፤ የንጉሠ ነገሥቱ ሊጋባ በቀለ በየነ ጠጋ ብለው ሹመት ወደሚሰጥበት "ዱክ ቤት" ወደተባለው አዳራሽ እንዲሄዱ ጠየቋቸው።

- ሊጋባው ፊት ፊት፤
- ጸሐፊ ትዕዛዝ ማህል፤
- ምክትሉ ሊጋባና ዋናው አጋፋሪ ከኋላ አጅበዋቸው፤

ዱክ ቤት በተባለው አዳራሽ ሲገቡ፤ በዚያ ቀደም ብለው ከተገኙት ከቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ጠቅላይ ሚኒስትር፤ ከራስ አበበ አረጋይ የአገር ግዛት ሚኒስትር፤ ከአቶ ገብረወልድ እንግዳ ወርቅ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ጋር የእጅ ሰላምታ ተለዋወጡ። ወዲያው፤ ሊጋባ በቀለ በየነ የሊጋባነት ዘንጋቸውን አንሥተው፤ " ክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ! " የሚል የጥሪ ድምፅ ሲያሰሙ፤ አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ ከንጉሠ ነገሥቱ የተሰጠውን የሹመት ትዕዛዝና መግለጫ ካነበቡ በኋላ፤ የቀድሞው የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር፤ ከዛሬው ዕለት ጀምሮ የአሩሲ (ዛሬ አርሲ) ጠቅላይ ገዥ ሆነው መሾማቸውን አበሠሩ። ከዚህ ቀደም ለሌሎች ተሿሚዎች ሆነ ተሻሪዎች ተደርጐ የማይታወቅ አዲስ ነገር ሆኖ የታየው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የአሩሲ ገዥ ሆነው የተሾሙበት ምክንያት ምን እንደሆነ፤ በሹመቱ ሥነ ሥርዓት ላይ መነገሩ ነው። አቶ ገብረወልድ ያነበቡት ቃል፤ ያው ጃንሆይ ጠዋት በአራት ሰዓት ተኩል ላይ አቡነ ባስልዮስ ባሉበት በአረንጓዴ ሳሎን የነገሯቸው ነው እንጂ፤ አዲስ ነገር አልነበረም። ይኸንኑም አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር፤ በታዘዙት መሠረት እንደ አዋጅ ቃል ያነበቡት የሚከተለውን ነበር።

---

* በዋናው የእልፍኝ አስከልካይ አስተያየት፤ ጸሐፊ ትእዛዝ ከጃንሆይ ጋር በፈለጉበት ጊዜና በፈለጉበት ሰዓት የጃንሆይን ቢሮ አንኳኩተው የሚገቡ ናቸው። አስኪጠሩ የሚጠብቁ አልነበሩም።

## ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሆይ!

1. ከዚህ ቀደም ልብህም፣ እግርህም፣ ስለራቀን ምን ሆነሃል? ብንልህ፤ ጥያቄያችን ሳይከብድህ ስለቀረና እውነተኛውን ምክንያት ገልጸህ ለመናገር ፈቃደኛ ስላልሆንክ፣

2. ሉንዶን ስንሄድ፤ እዚያው እናገራለሁ ያልከውንም ጉዳይ ሳትነግረን በመቅረትህ፤ ስለዚሁም ደጋግመን ብንጠይቅህም " ... ያንኑ የሥራ ጉዳይ በስደተኛ ቋንቋ ለመናገር ነበር እንጂ፤ ቢቀርም ፍሬ ነገር የለውም ብዬ ነው" የሚል የተሽፋፈነ ምላሽ ስለሰጠኸን፣

3. ሥራህን ችላ ማለትህንና ባሕሪህም ተለውጦ ስላገኘነው፣

4. ራስህን አሁን ከምታሳየው ሁኔታ ማረም የሚገባህ መሆኑን አይተን፤ ባሕሪህ እስኪሻሻል ድረስ፤ የሥራ ዝውውር በማድረግ፤ የአሩሲ (ዛሬ አርሲ) ጠቅላይ ገዥ ሆነህ እንድትሠራ አዘንሃል። ....

ጃንሆይ ቀደም አድርገው በአረንጓዴ ሳሎን የነገሯቸው፤ ይህ ከዚህ በላይ የተገለጸው የወቀሳ ቃል እንደገና በድጋሚ በአዋጅ መልክ በሹመቱ ሥነ ሥርዓት ላይ ሲነበብ፤ ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ምን ያህል ሞራልን የሚነካ መሆኑን መገመት ይቻላል። ሆኖም፤ አጅሬ ይህን ያህል የተነኩ መሆናቸውን በማሳየት ተቃዋሚዎቻቸውን ማስደሰት አልፈለጉም። የአቶ ገብረወልድ መግለጫ ሲፈጸም፤ ፊታቸውን ወደ ጠቅላይ ሚኒስትሩ መልሰው፤ " ... የጃንሆይ ነው ያላችሁት ቃል የናንተ ስለሆነ፤ ልቤ አይቀበለውም። በመጀመሪያ እኔ እንደእናንተው የጃንሆይ ታማኝ፤ የጃንሆይ ባሪያ ነኝ። አሁንም ነኝ። ወደፊትም ያው ነኝ። የጃንሆይን ትዕዛዝ ግን በደስታ ተቀብያለሁ ... " ብለው እጅ ነሥተው ወጡ።

ከዱክ ቤት መውጫ በር ላይ፤ በሊጋባ በቀለ በየነና በኮሎኔል መኰንን ደነቀ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ አማካይነት፤ ንጉሠ ነገሥቱንና ንግሥቲቱን ጫማ ለመሳም ወደ ገነተ ልዑል አረንጓዴ ሳሎን አመሩ። በዚህ ጊዜ በቤተመንግሥቱ ቅጥር ግቢ ውስጥ የሚታየው ትርምስ ከዚህ በፊት ታይቶ የሚታወቅ አይመስልም ነበር። ቁጥራቸው በርከት ያሉ የክብር ዘበኛ መኰንኖችና ወታደሮች፤ በጦር ልብስና በመሣሪያ ትጥቅ ሆነው፤ ቤተመንግሥቱን አጥለቅልቀውታል። ደጃዝማች መስፍን ስለሺ የቤተመንግሥቱ "ሎርድ ቻምበርሌን" በመሆናቸው፤ የጦር ልብስ ለብሰውና ቱራዠር አንዥርግገው፤ ሽጉጣቸውን ታጥቀው፤ ወደ አረንጓዴው ሳሎን መግቢያ ላይ ሲንጉራደዱ ይታዩ ነበር። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በግል ማስታወሻቸው ላይ የሽረቱ ዕለት የደረሰውን ሁኔታ ሲጠቅሱ፤ " ... የግቢው መናወጥ፣ የዘበኞቹ መደነባበር፣ የክብር ዘበኞች መሸባበር፣ የደጃች መስፍን ስለሺ ማገርገር ብዙ ነገር ያሳይ ነበርና ሥዕሉን ለመተረክ ላውሪ ያስቸግራል ... " ብለዋል። ጸሐፊ ትዕዛዝ እንዳሉት፤ በዚያን ዕለት በቤተመንግሥቱ ውስጥ የታየው መተረማመስ፤ ኩዴታ ተዘጋጅቶ የከሸፈ ወይም በመክሸፍ ላይ የሚገኝ ስለሚመስል፤ ከሰው ጋር በእርጋታ መነጋገርና እውነተኛው ምክንያት ምን መሆኑን ለማወቅ አስቸጋሪ ነበር። በሌላው ጊዜ ወደ ቤተመንግሥቱ ለመምጣት የተፈቀደላቸው ደጀጠኒዎች፣ እጅ ነሽዎች፣ የዙፋን ችሎት ባለጉዳዮች፣ በዚያን በሚያዝያ 17 ዕለት ወደ ግቢ እንዳይገቡ ተከልክለዋል። በዚያን ጊዜ እኔ ዘውዴ ረታ የቤተ መንግሥት ሪፖርተር (ጋዜጠኛ) ስለሆንኩ፤ ከፎቶግራፍ አንሺው ከአቶ ተስፋዬ ተቋመ ጋር እንደተለመደው ከጠዋቱ በሦስት ሰዓት አምሳለ ገነት ቤተመንግሥት ተገኝተን ነበር። ከጥቂት ደቂቃዎች በኋላ ዋናው የእልፍኝ

አስከልካይ ሁለታችንንም ጠርተውን፤ " ጋዜጠኛው ማስታወሻውን ይዞ እየተዘዋወረ መሥራት ይችላል። ፎቶግራፍ አንሺው ግን ለዛሬው ምንም ዓይነት ፎቶግራፍ እንዳያነሣ ስለተከለከለ ወደ ቤቱ ይመለስ " የሚል ትዕዛዝ ሰጡ። በዚህ መሠረት እኔ ከቤተመንግሥቱ ቆይቼ ለጸሐፊ ትዕዛዝ የተዘጋጀውን ፕሮግራም ስከታተል፤ ፎቶግራፍ አንሺው ወደ ዋናው መሥሪያ ቤት ተመለሰ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ሹመቱ ከተነገራቸው በኋላ፤ በአረንጓዴው ሳሎን አፕሬቲፍ ግብዣ ሲደረግ፤ ፎቶግራፍ እንዲነሣ የጃንሆይ መልካም ፈቃድ ሆነ። ነገር ግን አታስፈልግም ተብሎ ወደ ዋናው መሥሪያ ቤት የተመለሰው ተስፋዬ ተቋመ ከየት ይገኝ? .... ጃንሆይ በጣም ተቆጡ። በዚህ ጊዜ ኮሎኔል መኮንን ደነቀም ዓይናቸውን በእኔ ጋዜጠኛው ላይ ተክለው መዳነት ጀመሩ። ጥፋቱ የማስታወቂያ መሥሪያ ቤት ሆነ። እዚህ ላይ ዝም ማለቱ ጥፋቱን መቀበል ስለሆነብኝ፤ በድፍረት ወደ ጃንሆይ ጠጋ ብዬ፤ " ... ፎቶግራፍ አንሺውን አንተ አታስፈልግም ብለው ወደ መሥሪያ ቤቱ የመለሱት ዋናው የእልፍኝ አስከልካዩ ራሳቸው ናቸው .... " አልኩ። ጃንሆይ ቱግ አሉ። "አንተ እኮ ሥራህን አታውቀውም" ብለው ጮሁባቸው። መኮንን ደነቀ የሚሰጡት መልስ ስላልነበራቸው አቀርቅረው ዝም አሉ። ከጥቂት ደቂቃዎች በኋላ ፊታቸውን እንዳነበብኩት፤ በእኔ ላይ ምን ያህል ጥርስ እንደነከሱ በግልጽ ታየኝ። እንግዲህ፤ ከዚህ ስወጣ ቁጠኛው ኮሎኔል አንድ ነገር ሊያስደርጉኝ ይችላሉ ብዬ በመፍራት፤ ከአረንጓዴው ሳሎን ሳልወጣ እዚያው መቆየትን መረጥኩ። የጃንሆይ የእልፍኝ አሽከሮች ልጅ አድማሱ ረታ እና ልጅ መንገሻ ወልደማርያም ቀስ ብለው በጆርባዬ በኩል፤ " .... አይዞህ ዘውዴ አትፍራ! በመናገርህ ጥሩ አድርገሃል። ኮሎኔል ምንም አያደርግህም ... " ስላሉኝ፤ የሞራል ጥንካሬ አገኘሁ። እኔ እዚያው ከአረንጓዴው ሳሎን መግቢያ በር ላይ እንዳለሁ፤ አቶ መኮንን ሀብተወልድ በድንገት ከተፍ ብለው፤ የእልፍኝ አስከልካዩን ፎቶግራፍ አንሺውን ለምንድን ነው ያባረርከው? ብለው በቁጣ መንፈስ ጠየቋቸው። ኮሎኔልም፤ አዎን ጌታዬ ይቅርታ እጠይቃለሁ። በእኔ በኩል ዛሬ የተከናወነው ጉዳይ ፎቶግራፍ መነሣቱ አይጠቅምም ብዬ ነው .... በማለት የመለማመጥ መንፈስ ሲያሳዩ ሰማሁ። እኔም ይህን ካየሁ በኋላ፤ ዛሬ ከዚህ ግቢ በሰላም እንደምወጣ እርግጠኛ በመሆን፤ በጣም ተዝናናሁ። እውነትም ምንም የደረሰብኝ ነገር አልነበረም። የሆነ ሆኖ ዕድሜ ለኩሎኔል መኮንን ደነቀ፤ ከዚህ ቀደም በታሪክ ደርሶ ያልታየው፤ ለወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ በቤተመንግሥቱ የተዘጋጀው የሽረት ሥነ ሥርዓት፤ በፎቶግራፍ ዶክመንት ሳይያዝ መቅረቱ ያሳዝናል።

አሁን ወደ ጸሐፊ ትዕዛዝ ጉዳይ እንመለስና፤ ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ በዱክ ቤት የሹመቱ አዋጅ ከተነገረ በኋላ፤ አዲሱ የአሩሲ (አርሲ) ጠቅላይ ገዥ በሊጋባው፤ በዋናው የእልፍኝ አስከልካይና በዋናው አጋፋሪ ታጅበው፤ ንጉሠ ነገሥቱና ንግሥቲቱ በሚገኙበት አረንጓዴ ሳሎን ገብተው ጫማ ከሳሙ በኋላ፤ አፕሬቲፍ ግብዣ ተደረገ። በዚሁ ጊዜ ከጃንሆይና ከእቴጌ ጋር በአረንጓዴው ሳሎን የተገኙት ልዑል አልጋወራሽ፣ ብፁዕ አቡነ ባስልዮስ፣ ልዑል መኮንን፣ ልዑል ሣህለሥላሴ፣ ደጃዝማች መስፍን ስለሺ፣ የቤተመንግሥቱ ሎርድ ቻምበርሌንና የከፋ ጠቅላይ ገዥ፤ በወልደጊዮርጊስ ቦታ ጸሐፊ ትዕዛዝና የጽሕፈት ሚኒስትር ተብለው አዲስ የተሾሙት አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ ናቸው።

ለሐያ ደቂቃዎች ያህል በተከናወነው የአፕሬቲፉ ግብዣ ላይ፤ ንጉሠ ነገሥቱ የቀድሞውን ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ጠርተው በፈገግታ ለጥቂት ደቂቃ ሲያነጋግሯቸው ነበር። ነገር ግን ምን እንደተነጋገሩ የሰማ የለም። ከዚህ

በኋላ፤ የአሩሲው ጠቅላይ ገዥ ጃንሆይንና እቴጌን ተሰናብተው ከአረንጓዴው ሳሎን ሲወጡ፤ እንደ አመጣጣቸው በሊጋባው፤ በዋናው የእልፍኝ አስከልካይና በዋናው አጋፋሪ እስከ አውቶሞቢላቸው ድረስ የአሸኛኘት ሥነ ሥርዓት ተደረገላቸው። እንግዲህ፤ ለብዙ ወራት ሲፈተግና ሲታሽ የቆየው የወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከሥልጣን መውረድ፤ በዚች በሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም ሰኞ ከቀኑ በስድስት ሰዓት በሰላምና በፀጥታ ሲፈጸም፤ በሐያኛው ክፍለ ዘመን በተካሄደው የኢትዮጵያ ዘመናዊ ታሪክ ውስጥ ቦታ የሚሰጠው አንዱ ምዕራፍ እንደተዘጋ ተቆጠረ።

የምሳ ሰዓት ደርሶ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወደ መኖሪያ ቤታቸው ሲሄዱ፤ የተደረገውን ሹመት ቤተሰቦቻቸው አልሰሙም ነበር። ባለቤታቸው ወይዘሮ አልማዝ ይልማ ከብዙ ዓመታት በኋላ የሚያስታውሱትን እንደዳጫወቱኝ፤ በዚያች ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም ከቀኑ ሰባት ሰዓት ገደማ እቤት ሲገቡ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ምንም ዓይነት የብስጭት ወይም የማዘን ሁኔታ አይታይባቸውም ነበር። ለምሳ ገበታ ከመቅረባችን በፊት፤ " .... ስሚ! አልማዝ፤ ለሥራ ወደ አሩሲ እንድንዛወር ታዘናል። እንግዲህ! ስንቅ ማዘጋጀት ነው .... " የሚል ቃል ብቻ ተናገሩ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ከነበራቸው ሥራ ጃንሆይ ወደ ሌላ ቦታ እንደሚያዛውሯቸው ቀደም ብለው ጠርጥረው ነበር። ነገር ግን ያልደረሱበት የት ቦታ እንደሚያዛውሯቸውና ቀኑ መቼ መሆኑን ነው። ይህችም የተጠበቀች ቀን እንደምንም ደረሰች። ከዚህ በኋላ፤ ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሚቀራቸው የጽሕፈት ሚኒስቴር ሥራቸውን፤ ከእሱም ጋር ለአሥራ አራት ዓመታት ጠብቀው ያኖሩትን ታላቁን የንጉሠ ነገሥቱን ማሕተም ለአዲሶቹ ተሿሚዎች ማስረከብና፤ የአሩሲ ሕይወታቸውን አዘጋጅቶ መጓዝ ነበር።

## ዜናውን ለሕዝቡ ለማሰማት የተደረገ ዝግጅት

ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም

በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የተዘጋጀው የሹመት ሥነ ሥርዓት ከቀኑ በስድስት ሰዓት ላይ እንደተጠናቀቀ፤ በስምንት ሰዓት በራዲዮ የሚተላለፈውን ዜና ለማዘጋጀት ወደ ማስታወቂያ መሥሪያ ቤት መሮጥ ነበረብኝ። የሰርቪስ መኪናችን ሳይደርስልኝ ስለዘገየ፤ በዚያን ዘመን የነበረውን የሕዝብ ትራንስፖርት "ጋሪ" ፍለጋ ወዲያና ወዲህ ስል፤ ክቡር አቶ ሠረቀብርሃን ገብረእግዚእ፤ በዚያን ጊዜ የፖስታ ቴሌፎን ቴሌግራፍ ም/ሚኒስትር በአውቶሞቢላቸው ከግቢ ሲወጡ አፍንጫ በር ላይ አገኘኋቸው። እባክዎ ጌታዬ! የራዲዮ ሰዓት ሊያልፍብኝ ስለሆነ፤ አቡነ ጴጥሮስ ሐውልት ድረስ ይሸኙኝ? አልኳቸው። ምንም ሳያመነቱ አውቶሞቢላቸው ውስጥ ግባ አሉኝ። ለክብራቸው ብዬ ከሾፌራቸው ጐን ቦታ ያዝኩ። እሳቸው ከኋላ ናቸው። በጉዞአችን ላይ የእጅ ጣቶቻቸውን በማጮህ፤ ወይ ግሩም? ወይ ግሩም? እያሉ ብቻቸውን ሲነጋገሩ ሰማሁ። ፊቴን ወደ እሳቸው መለስ አድርጌ፤ ጌታዬ! በዛሬው ሹመት ተደስቱ? ወይስ አዘኑ? ብዬ ጠየቅኋቸው። ለመልሱ ጊዜ አልወሰዱም። " .... ሁለት ዓይነት ስሜት አድሮብኛል። በአንድ በኩል ስደሰት፤ በሌላ በኩል አዝኛለሁ። ያዘንኩት፤ ከእንግዲህ ወዲህ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የባለሚልነት ሥልጣን ብቻቸውን የሚይዙት እኝህ የአንተ አለቃ አስቸጋሪው መኰንን ሀብተወልድ ስለሚሆኑ፤ ምንም ዓይነት መሻሻል አይኖርም ብዬ ነው። የተደሰትኩት፤ የእኔን በግሪክ አገር ■■ባሳደር ሆኖ መሾም እስከዛሬ አግደው ያቆዩት ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ

በመሆናቸው፤ አሁን እሳቸው ስለተነቀሉ፤ ጃንሆይ ሹመቱን ያጸድቁልኛል ብዬ ተስፋ በማድረግ ነው አሉኝ። እኔም ቀጠልኩና ታዲያ ለአገር አስተዳደር ጉዳይ ጸሐፊ ትዕዛዝ ከአቶ መኰንን ይሻላሉ ማለት ነው? ብዬ ጠየቅኩ። ሠረቀብርሃን ገና ከመጀመሪያው መንፈሳቸው ግሎ ስለነበረ፤ አሁን ደግሞ በእኔ ጥያቄ ትኩሳታቸው 40 ሳያልፍ አልቀረም። እፊታቸው ላይ ቁጣና ብስጭት ይነበባል። " ... ስማ ዘውዴ! ሁለተኛ ይህን የመሰለ የመሃይም ጥያቄ እንድታቀርብልኝ አልፈቅድልህም። ስለዚህ ጉዳይ ከዚህ ቀደም ደጋግሜ አስተምሬህ ነበር። አዕምሮህ አልያዘውም ማለት ነው። አሁንም ደግሜ እነግርሀለሁ። በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና በአቶ መኰንን መካከል ምንም ልዩነት የለም። ሁለቱም በአሠራራቸው ሆነ በአስተሳሰባቸው ፍጹም ዲክታተሮች በመሆናቸው፤ ለአገር ሥልጣኔና ዕድገት እንቅፋቶች ናቸው። አሁን በዛሬው ቀን ጃንሆይ ከአንዱ ዋና አስቸጋሪ ከወልደጊዮርጊስ እንደተገላገሉት ሁሉ፤ ነገ ደግሞ ከሌላው ዋና አስቸጋሪ ከመኰንን ሀብተወልድም በቶሎ መገላገል አለባቸው። ወልደጊዮርጊስ ጤነኛ ስለሆኑ ወደ ጠቅላይ ግዛት ተልከዋል። አቶ መኰንን ሕመምተኛ ነኝ ስለሚሉ፤ በሚኒስትር ማዕረግ የአገር ፍቅር ማህበር ፕሬዚዳንትና የእስላሞች ጉዳይ አስፈጻሚ ተብለው፤ ከመንግሥቱ ካቢኔ መወገድ አለባቸው። እኔ ጃንሆይ ምን ታስባለህ? ቢሉኝ፤ የምመክራቸው ይህንኑ ነው ... " ንግግራቸውን ሳይጨርሱ አቡነ ጴጥሮስ ሐውልት ከማስታወቂያ መሥሪያ ቤት መግቢያ ላይ ደርሰን ሾፌሩ እንድወርድ በሩን ከፈተልኝ። ወዲያው እግዚአብሔር ይስጥልኝ ብዬ እጅ ስነሣ፤ የአውቶሞቢላቸውን መስኮት ከፍተው፤ " ... ማታ ከሥራ ስትወጣ በቀጥታ እኔ ቤት እንድትመጣ ... " አሉኝ። እኔ ከምኖርበት ከአባቴ ቤት፤ ከእሳቸው መኖሪያ ጐረቤት ስለሆንን፤ እቤታቸው የመሄድና አልፎ አልፎም አብሬአቸው ራት የመብላት ልማድ ነበረኝ። አሁን ግን ምንም ሳላደርግ፤ "መሃይም" ብለው ስለወረፉኝ፤ ሌላ ተጨማሪ ስድብ ለመቀበል አልሄድም ብዬ ቀረሁ። ሁለት ሳምንት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፤ ለሚያዝያ 27 ቀን የነፃነት በዓል፤ ግቢ አገኘኋቸው። ጠርቼህ ለምን ሳትመጣ ቀረህ? ብለው አልጠየቁኝም። እንዲያውም ከአሥር ቀን በፊት የነገሩኝን ሁሉ ሳይረሱት አልቀሩም። ዘውዴ! ና አሉኝና "ጌቶች ክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ እሁድ እሁድ በሀገር ፍቅር ማህበር ባለጉዳዮች የሚቀበሉበትን ሰዓት ጠይቀህ በቶሎ ንገረኝ" አሉኝ። እንደ አጋጣሚ የሀገር ፍቅር ማህበር ሥራ አስኪያጅ የሆኑት አቶ በሻህ ተክለማርያምን እዚያው ግቢ ስለአገኘኋቸው፤ እሳቸውን ጠይቄ ክቡር አቶ መኰንን ባለጉዳዮችን የሚቀበሉት በየሳምንቱ እሁድ ከዘጠኝ ሰዓት ተኩል እስከ አሥራ ሁለት ሰዓት ተኩል መሆኑን ነገርኳቸው። ወዲያው ክቡር አቶ ሠረቀ ንግግራቸውን በመቀጠል፤ " ... መቼም እንደ ጌቶች ክቡር አቶ መኰንንን የመሰለ አገር አፍቃሪ የለም። አንተም እሳቸው እጠገብ በመሥራትህ ጥሩ ዜጋ ይወጣሀል ... " የሚል ቃል ወረወሩ። እኔ በጣም ተገረምኩ። ከአሥር ቀን በፊት፤ አቶ መኰንን ያገር ዕድገት እንቅፋት ነበሩ። ዛሬ ደግሞ ጌቶች አቶ መኰንንን የሚያህል አገር አፍቃሪ የለም። "ሠረቀብርሃን ገብረእግዚእ ቀናተኛው ኢትዮጵያዊ" በዐሥር ቀናት ውስጥ ያደረጉት የአስተያየት ለውጥ በጣም አስደነገጠኝ። በኋላ ዘግይቼ ትክክለኛው ምክንያት ምን መሆኑን ተረዳሁ። በአቴና የግርማዊነታቸው ባለሙሉ ሥልጣን አምባሳደር ለመሆን በጣም ፈልገው ነበር። እሳቸው እንደሚሉት ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጉዳዩ እንዲዘገይ አግደውት ቆይቶ ነበር። አሁን ግን የሚፈልጉት እንዲፈጸምላቸው እሁድ እሁድ ሀገር ፍቅር ማህበር እየመጡ፤ ጌቶች ክቡር አቶ መኰንንን ደጅ ሲጠኑ ከሰነበቱ በኋላ፤ በጥቂት ወራት ውስጥ ያሰቡት ተፈጽሞላቸው ወደ አቴና ሄዱ። በእዚያም ሁለት ዓመት ያህል እንደሠሩ ባለመታደል በሕመም ከዚህ ዓለም በሞት ተለዩ። ሠረቀብርሃን ገብረእግዚእ ቀናተኛው ኢትዮጵያዊ እያሉ በፊርማቸው የሚገልጹት፤

ትክክለኛውን ከልብ የመነጨ ስሜታቸውን ነበር። ቁጡ ናቸው። ችኩል ናቸው። ስለ ኢትዮጵያ ላላቸው ፍቅር ግን ተወዳዳሪ አልነበራቸውም።

ወደተነሣሁበት ጉዳይ ልመለስና፤ ሠረቀብርሃን ከማስታወቂያ መሥሪያ ቤት ካደረሱኝ በኋላ፤ እቢሮዬ ገብቼ የዕለቱን ታላቅ ዜና እንደሚከተለው አዘጋጀሁ።

## ሹመት

ግርማዊ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልካም ፈቃዳቸው ሆኖ፤ ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም ዛሬ ከእኩለ ቀን በፊት በገነተ ልዑል ቤተመንግሥታቸው፤ ከዚህ የሚከተለውን ሹመት ሰጥተዋል።

1. የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር የነበሩት ክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የአሩሲ ጠቅላይ ገዥ (ዛሬ አርሲ)፣

2. የግርማዊነታቸው ልዩ ጸሐፊ የነበሩት አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ተብለው የጽሕፈት ሚኒስትር፣

3. ደጃዝማች መንገሻ ወልደጊዮርጊስ፤ የሕግ መወሰኛ ምክር ቤት አባል

የአዲስ አበባ ራዲዮ ለተሿሚዎቹ መልካም ምኞቱን ይገልጣል።

ይህ ዜና ከዚህ በላይ እንደታየው ከተዘጋጀ በኋላ፤ በደንባችን መሠረት የማስታወቂያ ቦርድ አባሎች እንዲያጸድቁት ስጠባበቅ፤ ከቀኑ ሰባት ሰዓት ተኩል ሲሆን አቶ መኰንን ሀብተወልድ ከፀጥታው ሹም ከኮሎኔል ለማ ገብረማርያም (ኋላ ብ.ጄ) ራዲዮ ጣቢያው መጡ። ወዲያው ያዘጋጀሁትን አሳየኋቸው። ጥቂት መልከት ካሉ በኋላ፤ የለም ዘውዴ! <u>ሌላ የተሰናዳ አለ። አንባቢውም አቶ ሳቡሬ እንዲሆን</u> ከቤቱ በአስቸኳይ ተጠርቶ ይምጣ፤ ብለው ትዕዛዝ ሰጡ። ተላላኪው አቶ አሐዱ ሳቡሬ ቤት ሄዶ እስኪጠራቸውና እሳቸውም እስከሚመጡ ድረስ፤ የዜና መስጫችን ሰዓት ይተላለፍና ሕዝቡን በአገር ላይ ምን ደረሰ? በማለት ሥጋት ላይ እንጥለዋለን ብዬ መጨነቄን ለክቡር አቶ መኰንን ነገርኳቸው። አቶ መኰንን በፈገግታ ካዳመጡኝ በኋላ፤ " ... **እይዞህ ዘውዴ! የወሬው ሰዓት ከወትሮው ልማድ ቢዘገይ፤ ሕዝቡ አንድ ትልቅ ወሬ ቢኖር ነው ብሎ ጆሮውን አንቅቶ ይጠባበቃል እንጂ፤ ሥጋት ላይ አይወድቅም። አንተ አትጨነቅ!** አሉኝ። ስምንት ሰዓት ከአምስት ደቂቃ ሲሆን፤ የዛሬይቱ ኢትዮጵያ ጋዜጣ ዋና አዘጋጅ አቶ አሐዱ ሳቡሬ ራዲዮ ጣቢያው ደረሱ። ወዲያው አቶ መኰንን ጠርተው ይህን ሹመት ተናገር! ብለው ከግቢ ተዘጋጅቶ ያመጡትን ወረቀት ሰጧቸው። ቃሉ የሚከተለው ነበር።

# ታላቅ ሹመት

በግርማዊ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልካም ፈቃድና ትዕዛዝ፤ ዛሬ ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም፡-

- ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤
  የአሩሲ ጠቅላይ ገዥ፣
- አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ፤
  ጸሐፊ ትዕዛዝ ተብለው የጽሕፈት ሚኒስትር

ሆነው ተሾመዋል፡፡

አሐዱ ሳቡሬ መድፍ በሆነው ድምፃቸው፤ ይህን ታላቅ ሹመት በስምንት ሰዓት ከአሥር ደቂቃ ላይ በራዲዮ ካነበቡ በኋላ፤ ሌሎቹን ዜናዎች ከአገር ውስጥና ከውጭ አገር የደረሱንን፤ የዕለቱ ተረኛ እኔ ስለሆንኩ መናገር ነበረብኝ፡፡ እንደተለመደው የቀኑ የራዲዮ ፕሮግራም በዘጠኝ ሰዓት የሚፈጸም ስለሆነ፤ በመጨረሻው ደቂቃ ላይ ታላቁ ሹመት ተደግሞ እንዲነበብ አቶ መኩንን አዘዙ፡፡ ለሁለተኛው ንባብ አቶ አሐዱ ስላልተገኙ፤ እኔ ተረኛው እስፒከር እንድናገር ተፈቅዶ፤ ድምጼን ጉላ አድርጌ ለማሰማት የተቻለኝን አደረግኩ፡፡

የራዲዮ ፕሮግራሙን ፈጽሜ በዘጠኝ ሰዓት ተኩል ወደቤቴ ስሄድ፤ "ፒያሳ" ከሚባለው በማህል አራዳ በኩል አለፍኩ፡፡ በዚያ በልዩ ልዩ ሥፍራዎች የተተከሉትን የራዲዮ የድምፅ ማጉሊያዎች (Loud Speaker) ዙሪያቸውን ከበው የተሰበሰቡት ሰዎች በጣም ብዙ ሆነው አየኋቸው፡፡ ሰዎቹ የሚጠብቁት ወሬው እንደገና ይነገራል ብለው ነው፡፡ አብዛኛዎቹም ከየመሥሪያ ቤታቸው ሳይታዘዙ ወይም ሳያስፈቅዱ የመጡ በመሆናቸው፤ ወደየሥራቸው ለመመለስ አልፈለጉም፡፡ መቸም በየሱቁ ከሚነግደውና በየመንገዱ ከሚተላለፈው ሕዝብ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን በዝና ማን መሆናቸውን የሚያውቅና ዛሬ ስለ እሳቸው በራዲዮ የተነገረው ሹመት ወይም ሽረት መሆኑን መለየት የሚችለው ይኸው የመንግሥት ሠራተኛው ስለሆነ፤ ብዙ ዓይነት ትችት የሚደረገውም በዚሁ ሠፈር ነበር፡፡ የማስታወቂያ መሥሪያ ቤት የሥራ ጓደኛዬን አቶ ይልማ ገብረወልድን በድንገት እዚያው "ፒያሳ" አግኝቼው፤ ወደ ሕዝቡ ጠጋ ብለን ከአንዳንዶቹ የሚረወረውን አስተያየት ለማዳመጥ ሞከርን፡፡ አንዳንዱ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ከጃንሆይ ጋር እንግሊዝ አገር በነበሩ ጊዜ ከጠቅላይ ሚኒስትሩ ከቸርችል ጋር የምሥጢር ንግግር በማድረጋቸው ነው ሲል፤ ሌላው ደግሞ፤ ለጃንሆይ አልታዘዝም ብለው ስለአስቸገሩ ነው ይላል፡፡ በጣም ጥቂቶች የሆኑት ደግሞ እንግሊዝ አገር ብዙ ሚሊዮን ብር ለምን አስቀመጥክ? ብለው ጃንሆይ ስለተጣሏቸው ነው የሚል ሐሳብ ይሰነዝራሉ፡፡ በጠቅላላው፤ አቶ ይልማ ገብረወልድና እኔ እንደሰማነው፤ ይህ ሁሉ አስተያየት ከፈጠራ የመነጨ እንጂ፤ አንዳች መሠረት የጨበጠ አልነበረም፡፡ በዚህ በተደረገውም ሹመት፤ ለሕዝቡ ምን እንደሚጠቅመውና ምን እንደሚጎዳው፤ የመመራመር ወይም የማወቅ ፍላጎት እንደሌለ ግልጽ ነው፡፡ ሆኖም፤ በዚህች በሚያዝያ 17 ቀን የፈነዳው ሹመት፤ ቀጥታ የሚመለከተውንም ሆነ የማይመለከተውን፤ ከፍ ያለ ድንጋጤ ላይ እንደጣለው በትክክል ታይቷል፡፡

# ጸሐፊ ትዕዛዝ! እንኳን ደስ አለዎ?
# ወይስ እምላክ ያበርታዎ?

ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፣ ሹመቱን ከተቀበሉና በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት በአረንጓዴ ሳሎን የአፕሬቲፍ ግብዣ ከተደረገላቸው በኋላ፣ ወደ መኖሪያ ቤታቸው ተመልሰው እንኳን ደስ አለዎ ለማለትም ይሁን፣ ወይም ደግሞ አምላክ ያበርታዎ የሚል መልካም ምኞት ለመግለጥ የመጡትን ወዳጆችና ዘመዶች ተቀብለዋል። በልማድ እንደሚታወሰው፣ አንዳንድ ያልተደሰቱ ወይም ያዘኑ ተሿሚዎች እንደሚያደርጉት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ እንግዶች አልቀበልም ብለው የቤታቸውን በር አልዘጉም። ይህን ቢያደርጉ፣ ተሳሳቱ ወይም ልክ አይደሉም የሚላቸው አይኖርም ነበር። እሳቸው ግን፣ የንጉሠ ነገሥቱን ሹመት መቀበላቸውን ማሳየት እንጂ፣ በተሰጣቸው ሥራ አለተደሰትኩም ብለው ስሜታቸውን መግለጥ አልፈለጉም።

ይሁን እንጂ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ብዙ ሰዎችን ታዝበዋል። በማናቸውም መልክ (ለማዘንም ሆነ ለማጽናናት) ሊጠይቋቸው እቤታቸው የመጡት የካቢኔ ሚኒስትሮች ሦስት ብቻ ናቸው። እነዚህም፦ ባላምባራስ ማኅተመሥላሴ ወልደመስቀል የእርሻ ሚኒስትር፣ አቶ አካለወርቅ ሀብተወልድ የትምህርት ሚኒስትር፣ አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ናቸው። ከአገረ ገዥዎች፣ ከአሩሲ ተሽረው ቦታውን ለጸሐፊ ትዕዛዝ የለቀቁት ደጃዝማች መንገሻ ሥዩም (ኋላ ልዑል ራስ) የአዲስ አበባ ከተማና የአውራጃዋ ገዥ ደጃዝማች ከበደ ተሰማ መጥተዋል። ከእነዚህ በስተቀር፣ ሌሎቹ የካቢኔ ሚኒስትሮችና እንዲሁም በከተማው የነበሩ አንዳንድ ጠቅላይ ገዥዎች ሳይጠይቋቸው በመቅረታቸው ጸሐፊ ትዕዛዝ ገልጠው ባይናገሩትም፣ ምን ያህል እንዳስገረማቸው መገመት ይቻላል። ንጉሠ ነገሥቱ እንኳ፣ እንደዚህ ባልጠበቁት ሁኔታ ከነበሩበት ሥልጣን ቢያነሷቸውም፣ በሹመታቸው ዕለት ለእንግዶች መቀበያ ብለው ከቤተመንግሥቱ የተዘጋጀ መስተንግዶ ልከውላቸዋል።

በሹመቱ ማግሥት ማክሰኞ ሚያዝያ 18 ቀን 1947 ዓ.ም ከጠዋቱ በሦስት ሰዓት፣ አዲሱ የአሩሲ ጠቅላይ ገዥ ብቻቸውን በእጃቸው አንድ ማስታወሻ ይዘው እጅ ለመንሣት ቤተመንግሥት በመጡ ጊዜ፣ የተደረገላቸውን የቀዘቀዘ አቀባበል ስመለከት፣ በዚያን ዘመን በእኔ በትንሹ ጋዜጠኛ አስተያየት እንኳ ከፍ ያለ የሐዘን ስሜት አደረብኝ። ከዚህ ከታሪካዊው ቀን ከሚያዝያ 17 በፊት፣ ዓይኔ ይመለከት የነበረውና የለመድኩት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ከጽሕፈት ሚኒስቴር ቢሮአቸው ተነሥተው ወደ ቤተመንግሥት ለመምጣት የእግር ጉዞ ሲጀምሩ፣ ገና ከሩቁ አጃቢዎቻቸው ምን ያህል ድምቀት ይሰጡ እንደነበረ፣ ከዚያም አምሳለ ገነት አደባባይ ሲደርሱ ደግሞ፣ እሳቸውን እጅ ለመንሣት የሚሽቀዳደሙትና የጋለ ትሕትናቸውን እንደ እስክስታ ወራጆች የሰውነታቸውን መሽቆጥቆጥ ለማሳየት የሚታገሉት የመንግሥት ባለሥልጣኖች፣ ደጀጠኒዎችና ባለጉዳዮች ምን ያህል ብዙዎች እንደነበሩ ሳስታውስ፣ ይህ ሁሉ በአንድ ቀን ዕድሜ ተለውጦ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የሚያህል ሰው፣ እንደሌላው ባለጉዳይ ሁሉ ንጉሠ ነገሥቱን እጅ ለመንሣት አደባባይ ላይ ቆመው ሲጠባበቁ በማየቴ እኔም በአቅሜ የተለየ ሐዘን ተሰማኝ። ይህም ያየሁት ሁኔታ፣ የዚህን ዓለም የሰዎችን ተለዋዋጭነትና ከንቱነት የሚያስገነዝብ በመሆኑ፣ ለምን ጊዜውም ከአዕምሮዬ ተቀርፆ ይኖራል።

# ምዕራፍ Ĩ

# የጃንሆይና የወልደጊዮርጊስ ተገላልጦ መነጋገር

## አቡነ ባስልዮስ ባሉበት

" .... ያሳደግኩትን አበባ እኔው
ቀርጨ መጣሉ ስለሚያሳዝነኝ፤
ይህ እንዳይደርስብኝ ተጠንቀቅ! ..."

(ቀ.ኃ.ሥ 1927 ዓ.ም)
አዲስ አበባ "ዱክ ቤት"

" ... ጃንሆይ፤ እንኳንስ ያሳደጉትን፤
የቆረጡትንም ቢሆን የመጣል ባሕርይ
እንደሌለብዎ ባሪያዎ ሆኜ በመኖር፤
ያየሁ ምስክር ነኝ ... "

(ወ.ጊ.ወ.ዮ.)
(ሎንዶን 1931 ዓ.ም)

እነዚህ ከዚህ በላይ የሠፈሩት ሁለት ጥቅሶች፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ በተለያዩ ጊዜያቶች የተለዋወጧቸው አስተያየቶች ናቸው። ከግራ ወደ ቀኝ የመጀመሪያው፤ እንደ ኢት. አቆ. በ1927 ዓ.ም ንጉሠ ነገሥቱ ወልደጊዮርጊስን የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ብለው ሲሾሟቸው፤ በዚያች የሹመት መስጫ በሆነች "ዱክ ቤት" ውስጥ የሰጧቸውን ምክር ነው። ሁለተኛው፤ ወልደጊዮርጊስ በስደቱ ዘመን በ1931 ዓ.ም ሎንዶን ሆነው፤ ይህንን ከንጉሠ ነገሥቱ የተሰጣቸውን ምክር አስታውሰው፤ ለጃንሆይ በጽሑፍ ከገለጹት አስተያየት ላይ የተወሰደ ቃል ነው። ከሐያ ዓመታት በኋላ የታሪኩ ሂደት ሲታይ፤ (1927-1947) ጃንሆይ የተናገሩት ደርሶ በተግባር ውሏል። የወልደጊዮርጊስ ተስፋ ግን እንዲሁ ተስፋ ሆኖ ቀርቷል።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፤ ሚያዚያ 17 ቀን ወደ አሩሲ ከተሾሙ በኋላ፤ ብቻቸውን ሲያስቡና ሲያጠኑ፤ ጃንሆይን በልዩ ቀጠሮ አግኝቼ የልቤን አውጥቼ መነጋገር ያስፈልገኛል አሉ። ይኸውም ጃንሆይ ባላሰብኩትና ባልጠበቅኩት መንገድ እስከዚህ አርቀው የጣሉኝ ምን ባጠፋ? ምን ብበድል? ምን ባስቀይም? እንደሆነ፤ እውነተኛውን ምክንያታቸውን ገልጠው እንዲነግሩኝ እፈልጋለሁ። እርግጥ ነው! ከዚህ በፊት በተለይ ሽረቴን ራሳቸው በነገሩኝ ዕለት፤ "እግርህም ልብህም ስለራቀን፤ ሥራህንም ችላ ስላልከው" የሚል ምክንያት ነግረውኛል። ይሁን እንጂ፤ በእኔ ላይ በአንድ ጊዜ ይህንን ከባድ እርምጃ ለመውሰድ የተነገሩኝ ምክንያቶች በቂ አይደሉም። ሌሎች የተደበቁ ነገሮች ይኖራሉ። ስለዚህ፤ ጃንሆይን ግልጽና እውነተኛ በሆነ መንገድ አነጋግሮ መረዳት በጣም አስፈላጊ ነው። ይህንን ሁሉ ጠይቄ ከጃንሆይ የሚሰጠኝ መልስ የሚያረካኝ ካልሆነ፤ ወይም የሚያሳዝነኝ ከሆነ፤ ለጃንሆይ መንግሥት ሸክም መሆንን ስለማልፈልግ፤ የሥራ ስንብት እንዲሰጠኝ አመልክቼ፤ እያረስኩም ሆነ እየነገድኩ እነዚህን ሦስት ራስ ያልቻሉ ልጆቼን ማሳደግ እመርጣለሁ በሚል አስተሳሰብ፤ አዕምሮዋቸውን ከአዘጋጁት

በኋላ፤ ጃንሆይን በቆይታ ለማነጋገር ልዩ ቀጠሮ እንዲሰጣቸው ሊቀ ጳጳሱን አማላጅ ላኩ።

ቀጠሮው ተጠይቆ ቀኑ ከመወሰኑ በፊት፤ አንድ በጣም ለሚያምኗቸው የቤተሰቡ ወዳጅ ለሆኑት ሰው ያቀዱትን ሐሳብ ገልጠው ሲያማክሯቸው፤ እኚህ ወዳጅ ደግሞ ከልባቸው የሚያስቡትን እንደሚከተለው ነገሯቸው።

" ... በዚህ መንፈስና በዚህ አኳኋን ጃንሆይን ማነጋገር ምን ጣጣ እንደሚያስከትል፤ ምን ችግር እንደሚፈጥር ግልጽ ሆኖ ይታየኛል። ስለዚህም፤ ሐሳቡን ጨርሶ አልደግፈውም። ለእነዚህ ራስ ላልቻሉ የሰባት፣ የሦስትና የአንድ ዓመት ዕድሜ ላላቸው ልጆች፤ ማሰብና ቅድሚያ መስጠት ተገቢ መሆኑን የምንስማማበት ከሆነ፤ ያለ አንዳች ክርክር፤ ያለ አንዳች ውዝግብ፤ የንጉሠ ነገሥቱን ትዕዛዝ ተቀብሎ መፈጸም ግዴታ ይሆናል። በዚህ ዓለም ብዙውን ጊዜ የሰው ልጅ ላፈራቸው ልጆቹ መሥዋዕትነትን መቀበል የተለመደ እንጂ አዲስ ነገር አይደለም። ንጉሠ ነገሥቱ፤ ጸሐፊ ትዕዛዛቸውና የቀኝ እጃቸው የነበረውን ሰው ሲሸሩ፤ ጊዜ ወስደው አስበውበትና ተደራጅተውበት ነው። ወልደጊዮርጊስ ግን፤ ይህን የመሰለው አደጋ እንደሚወድቅበትና እንደሚጐዳው፤ ሳይጠረጥርና ሳይሰናዳ ነው። ስለዚህም፤ ሳያስበውና ሳይጠብቀው የደረሰበትን በቆራጥነትና በአርቆ አስተዋይነት መንፈስ ከመቀበልና የደንቡን ከመፈጸም በስተቀር፤ ሌላ ምርጫ እንደሌለው መወሰን አለበት። ምንም እንኳ፤ ዕውቀትና አገልግሎት የሠራተኛ መለኪያና መመዘኛ መሆናቸው ባይካድም፤ በአንዳንድ አስተዳደር ደግሞ፤ ድህነትም ለጥቃት አመቺ መሆኑ መዘንጋት የለበትም። በእኔ ሐሳብ ከጃንሆይ ጋር ለመነጋገር የተጠየቀው ቀጠሮ፤ አንድ ጊዜ ተጠይቋልና መከበር አለበት። ነገር ግን፤ በቀጠሮው ዕለት የሚደረገው ንግግርና የሚቀርበው ሐሳብ፤ አንዳች ችግር ሊያስከትል የሚችል እንዳይሆን በብርቱ ሊታሰብበት ይገባል .... " ሲሉ የጸሐፊ ትዕዛዝ የልብ ወዳጅ ምክራቸውን ለገሡ።*

ጸሐፊ ትዕዛዝ በረጋ መንፈስ ሲያስቡበት፤ የእነዚህ የሦስት ትንንሾች ልጆች ጉዳይ እጅግ የሚያስጨንቅ ሆኖ አገኙት።

ከጠላት ወረራ በፊት የወለዷቸውን ሦስት ሴቶችና ሁለት ወንዶች ልጆች ከእናታቸው ጋር ለወንድማቸው አደራ ሰጥተው ጃንሆይን ተከትለው ወደ ማይጨው ዘመቻና ከዚያም ወደ ስደት ሲሄዱ፤ ያደረጉት ውሳኔ ምን ያህል የሚያሳዝንና የሚያስቸግር እንደነበረ ትዝ አላቸው። ያን ጊዜ እንኳ፤ በልጆቼ ላይ ያስጨከነኝ ያገር ጉዳይ ሆኖ ነው። አሁን ግን፤ ተናግረህ አስቀይመሃል ወይም ተዳፍረሃል ተብዬ ብጋዝና ብጉሳቆል፤ በእኔ ምክንያት እነዚህ ሕፃናቶች ለምን ይቸገሩ ? ለምንስ ይሰቃዩ ? ብለው አመዛዘኑ። ስለዚህ፤ በጠየቁት ቀጠሮ ንጉሠ ነገሥቱ በሚቀበሏቸው ጊዜ፤ ምንም በልባቸው የሚያስቡትን ሁሉ የመከራው ዘመን አገልጋይነታቸውን እየተመረኮዙ ከማስረዳት መቆጠብ ባይፈልጉም፤ በተቻለ መጠን የጃንሆይን ይቅርታ ለማግኘት እንጂ፤ ጃንሆይ ያሳደሩትን ቅሬታ ለማባባስ መሆን እንደሌለበት አምነው፤ የሚሰጣቸውን ቀጠሮ በመጠባበቅ ላይ ቆዩ።

---

* እኚህ የልብ ወዳጅ የተባሉት ፊታውራሪ ፀሐዩ እንቁሥላሴ (ኋላ ደጃዝማች) መሆናቸውን ጄኔራል መኮንን ደነቀ ነግረውኛል።

ሚያዝያ 27 ቀን 1947 ዓ.ም አሥራ አራተኛው የነፃነት ድል በዓል በተከበረበት ዕለት፣ የቀድሞው የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር፣ አዲሱ የአሩሲ ጠ/ገዥ በታላቁ የዳግማዊ ምኒልክ ቤተመንግሥት አዳራሽ በተዘጋጀት የሻምፓኝና

የራት ግብዣዎች ላይ ተካፋይ እንዲሆኑ ተጠርተው ነበር። ከጥቂት ቀናት በፊት፣ ከአዲስ አበባ ከንቲባነት ወደ ሸዋ ጠቅላይ ግዛት እንደራሴነት የተሾሙት ደጃዝማች ከበደ ተሰማ፣ በበዓሉ ዋዜማ አንዲት ማስታወሻ ለጃንሆይ ላኩ። " ... ነገ በምናከብረው የነፃነታችን በዓል ላይ ተካፋይ እንዲሆኑ በግርማዊነትዎ መልካም ፈቃድ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ መጠራታቸውን ሰምቼ ደስ ብሎኛል። ስለዚህም፣ የፕሮቶኮል አቀማመጣቸው ወደ ጠቅላይ ገዥነት ከመዛወራቸው በፊት የነበረውን ደረጃ ቢይዝ፣ ተመልካች ሁሉ የጃንሆይን ልግሥና እንደሚያደንቅ፣ ባሪያዎ ለግርማዊነትዎ ማሳሰብ ግዳጄ መስሎ ታይቶኛል ... " ሲሉ ያመለከቱትን፣ ንጉሠ ነገሥቱ እንዲፈጸም አዘዙ። በዚህ መሠረት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ለሻምፓኙ ግብዣ ከታላቁ ቤተመንግሥት በሞርኒንግ ልብስ ሲደርሱ፣ በፊት እንደሚደረገው ዋናው የእልፍኝ አስከልካይ ተቀብለው፣ ሚኒስትሮች በሚቆሙበት መስመር ከጄኔራል አቢይ አበበ ቀጥሎ፣ ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ በላይ፣ የነበራቸውን የቀድሞ የፕሮቶኮል ቦታቸውን ሰጧቸው።

ከአሩሲው ሹመት በኋላ፣ ሁለቱ የጥንት ወዳጆች ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ የሚገናኙት ለመጀመሪያ ጊዜ ስለሆነ፣ ቀዝቀዝ ያለ የእጅ ሰላምታ ሲለዋወጡ፣ በአዳራሹ የነበሩት ሁሉ በአንክሮ ሲመለከቷቸው ይታይ ነበር። ከጥቂት ደቂቃዎች በኋላ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ፊታቸውን ወደ አቶ መኰንን መለስ አድርገው፣ " ... ምነው ወንድሜ ተሾሜ እንኳን ደስ ያለህ ሳትለኝ ቀረህ ? ... " ብለው ጠየቋቸው። አቶ መኰንን ግልጽ የሆነ መልስ ስላልሰጧቸው፣ " ... እንግዲያውስ! እኔ አንተን እንኳን ደስ አለህ ለማለት እቤትህ እመጣለሁ ... " አሏቸው። ለዚህም፣ አቶ መኰንን መልስ መስጠትና ንግግሩን መቀጠል አልፈለጉም። ከዚህ በኋላ፣ በዓሉ እስከተፈጸመ ድረስ ሁለቱም ሳይነጋገሩ ተለያዩ።

ዓርብ ሚያዝያ 28 ቀን 1947 ዓ.ም ከጠዋቱ በ፬ ሰዓት፣ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት በተለመደው አረንጓዴ ሳሎን፣ ንጉሠ ነገሥቱ አቡነ ሳስልዮስ ባሉበት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ጠርተው አነጋገሯቸው። ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ ቀጠሮውን የጠየቁት ባለጉዳዩ ጸሐፊ ትዕዛዝ ስለሆኑ፣ ዋና ዋና ሐሳባቸውን ነጥብ በነጥብ የገለጹት እንደሚከተለው ነበር።

- የጃንሆይ የቅርብ አገልጋይ በመሆኔ፣ ስሾምም እንደ ልጅ ማበረታቻ ተሰጥቶኝ፣ ስሻርም እንደ ልጅ ማረሚያ ተነግሮኝ ስለሆነ፣ ለተሰጠኝ ዕድል ምስጋናዬን አቀርባለሁ።

- ቅሬታችንን ከምንም አልቆጠርከውም ብለው ጃንሆይ ወቅሰውኛል። ዛሬ ለጃንሆይ የምናገረው እውነተኛውን ነው። ጃንሆይ ቅሬታ ያሳደሩብኝ መሆኑን፣ እንደ ወትሮው ገልጠው ካልነገሩኝ፣ ወይም ካልገሠፁኝ፣ እንዴት አድርጌ ልጠርጥር? ... አንዳች ነገር ሲጉድልብኝ አላየሁም። ለበዓል ሆነ ለጾም ሳልዘነጋ፣ ችሮታዎ ያልተለየኝ ነኝ። በሥራዬም በማቀርበው ሐሳብ፣ በሚሰጡኝ መምሪያ ከወትሮው የተለየ ሁኔታ

አልገጠመኝም። እንግዲያውማ ቅሬታ ያሳደሩብኝ መሆኑን ባውቅ ኖሮ ቅሬታውን ለመግፈፍ አልሠዋም ነበር?

- በሎንዶን አመለክታለሁ ብዬ የነበረውም፤ ከዚህ ቀደም ባጭሩ እንደገለጽኩት፤ በዚያ በስደቱ ጊዜ ጃንሆይ ያሳለፉትን የመከራ ዘመን በማስታወስ፤ አንዳንድ ለአገር ጠቃሚዎች የሚመስሉኝን ሐሳቦች አዘጋጅቼ ለማቅረብ ነበር። ኋላ ግን በሌሎች ሥራዎች በመጠመድ ያሰብኳቸውን ሳልነድፋቸው ወይም ሳላዘጋጃቸው በመቅረቴ ነው እንጂ፤ ሌላ ነገር ሆኖ አልነበረም።

- ጃንሆይ ከፈቀዱልኝ፤ በልቤ ላይ የሚንቀዋለለውን ሐሳብ ሁሉ መግለጥ እወዳለሁ። እኔም ሆንኩ ሌላው ታማኝ አገልጋይዎ፤ በጃንሆይ ቻኘነት ተመክተንና አምነን የምንኖር ስለሆነ፤ ሌሎች ክፉዎች በስምዎ ግፍ እንዳይሠሩ አደራዬን አጠብቃለሁ። በእኔ በኩል ሕይወቴ መልካም ነው የምለው፤ በጃንሆይ ክፉ ሲደርስ አለማየትን፤ ለሐዘን ምክንያት አለመሆንን ነው። ከዚህ ቀደም መላልሼ እንደተናገርኩት፤ አዬ ጌታዬ! የሚያሰኝ ጊዜ አያድርሰኝ እያልኩ ፈጣሪዬን እለምናለሁ።

- የጃንሆይ መንግሥት፤ አባቴን፣ ወንድሜን፣ ልጄን የገበርኩለት ነው። እኔም ከማናቸውም ሳልቆጠብ፤ መሥዋዕትነትን የተቀበልኩበት መንግሥት ነው። የቤተሰቦቼ ዕድል በጠላት ጊዜ መሰቃየትና ሞት ስለነበረ፤ በጃንሆይም መንግሥት ችግርና መከራ እንዳይገጥማቸው፤ ሰብሳቢም እንዳያጡ፤ ጃንሆይ እንዲያስቡልኝ እለምናለሁ።

- አንድ ጃንሆይን ብቻ በማመን፤ እግዚአብሔር የበለጠ እንደሚያውቀኝ ሳምን፤ ጃንሆይ ደግሞ ከዚህ የበለጠ ያውቁኛል ብዬ ያደላሁ ፍጡር ነበርኩ። የሰጡኝን አደራ መውሰድ ግን፤ የጃንሆይ ፋንታ ነው።

ጃንሆይ! እርስዎ አሽከር አያጡም። እኔ ግን ጌታ አላገኝም። አሁን!

- ይውደዱኝ አልልም! አይጥሉኝ።

- ይመኑኝ አልልም ! አይጠርጥሩኝ።

- ይዘኑልኝ አልልም ! አይጨክኑብኝ።

ብዬ ትክክለኛውንና ከልቤ የማስበውን ገልጨልዎታለሁ። ዛሬ ያለፈው የ35 ዓመታት የአገልግሎት ሞያዬ የተናደበት ጊዜ ነው። ሆኖም የዚያ የመከራና የሐዘን ዘመን አገልጋይዎ የነበርኩ መሆኔን እንዲያስቡልኝ እለምንዎታለሁ።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ እነዚህን ነጥብ በነጥብ የገለጿቸውን ሐሳቦች ካደመጡ በኋላ፤ " ... ከሁሉ በፊት የብዙ ዓመታት የአገልግሎት ቅርስ እንዳለህ የታወቀ ነው። ... በሎንዶን እናገራለሁ ብለኸው የነበረው ሐሳብ፤ ይህ አሁን ያልከው መሆኑን አንተው ካላስረዳኸን፤ እኛ መልዓክ

አይደለን፤ እንዴት ማወቅ እንችላለን? ... ሌላው፤ ሰው እንዳያጠፋኝ ላልከው፤ ሰው ማለት አንተም ራስህ ነህ። ስለዚህ፤ ራስህ ራስህን እንዳያጠፋው ተጠንቀቅ።

ሁሉም ወደፊት በምትሠራው ይታያል ... " ሲሉ መለሱ። ጸሐፊ ትዕዛዝ በጣም ከሚያውቋቸው ንጉሠ ነገሥት ይህ የተሰጣቸው መልስ የነበረውን ቅሬታ የደመሰሰ ቸርነት ሆኖ አላገኙትም። ስለዚህም፤ " .... እኔ የጃንሆይን መቀየም ይዤ እንዴት ወደ ሥራዬ መሄድ እችላለሁ? ... " ብለው ጠየቁ። በዚህ ማህል ሊቀ ጳጳሱ ገብተው፤ " ... ጃንሆይ እኮ የተናገሩት እንደ ምሕረት ቃል የሚቆጠር ነው ... " አሉ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ግን፤ እውነተኛውን ከጃንሆይ በቀጥታ ለመስማት ጥያቄያቸውን ስለአጠነከሩ፤ ጃንሆይ እንደገና ትንሽ ግልጽ በሆነ መንገድ መለሱላቸው።

" .... ያለፈው አገልግሎትህ የሚፋቅ አለመሆኑን ነግረንሃል። አሁንም እንደግመዋለን። በቅርቡም ለፍርድ ሚኒስቴር ሥራ ማሻሻያ ሠርተህ ያቀረብከው ሐሳብ በጣም ጠቃሚ ነው። ወደፊትም በሥራ ላይ እንዲውል እናደርጋለን። እንግዲህ ማንኛውም ነገር ማለፊያ ስለሆነ፤ ቅሬታችንን እናወርዳለን። ወደፊትም ብትርቀን አንተው ነህ። ብትቀርበንም ያው አንተው ነህ .... " በሚል ንጉሣዊ ቃል ሰላም ወርዶ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የአሩሲ ጉዞአቸውን ማዘጋጀት ጀመሩ።

ለዚህ ለአሥረኛው ምዕራፍ ርዕሱ የተሰጠው፤ የጃንሆይና የወልደጊዮርጊስ ተገላልጦ መነጋገር የሚል ቢሆንም፤ ተገላልጦ ለመነጋገር ወልደጊዮርጊስ በተቻላቸው ሙከራ ማድረጋቸውን እንጂ፤ የጠበቁትን ያህል ውጤት አለማግኘታቸው ግልጽ ነው። እንደታየው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በሐሳብ አገላለጻቸውም ሆነ በአቀራረባቸው ብርቱ ጥረት ያደረጉት፤ ንጉሠ ነገሥቱ ይህንን በማንም ዘንድ ያልተጠበቀ ከባድ እርምጃ የወሰዱባቸው፤ ትክክለኛው ምክንያት ምን መሆኑን እንዲገልጹላቸው ነበር።

ጃንሆይ ግን፤ የወልደጊዮርጊስ ፍላጎት ምን መሆኑን ቢረዱትም፤ "የሻርኩህ በዚህ ጥፋትህ ነው" ብለው ሊገልጹላቸው አልፈለጉም። መቸም በጃንሆይ ቦታ ሆኖ ጉዳዩን ለተመለከተው፤ "የሻርኩህ የሥልጣን አረማመድህ የሚያሠጋ ስለሆነብኝ ነው .... " ብለው በግልጽ ይነግሯቸዋል ተብሎ አይጠበቅም። ሆኖም፤ ከእንግዲህ ወዲህ በእኛ በኩል ቅሬታችንን አውርደናል። ለወደፊቱም ብትርቀንም አንተ ነህ፤ ብትቀርበንም ያው አንተ ነህ፤ ሲሉ የተናገሩት ቃል የመልካም ግንኙነት ዕድል መኖሩን የሚመለከት ስለሆነ፤ ንጉሠ ነገሥቱና የቀድሞው ጸሐፊ ትዕዛዛቸው በዚህ በሚያዝያ 28 ቀን 1947 ዓ.ም ሐሳብ መለዋወጣቸው የሚጠቅም እንጂ የሚከፋ አልሆነም።

# ምዕራፍ ፲፩

## የመጨረሻው ስንብት
## በፍጥነት ወደ አሩሲ !

" ... ሰው የዋህ ነው፣ ድልል ነው፣ ይኸ ይደርስብኛል ብዬ አላሰብኩም ነበር። ትልቁ ስሕተቴ እዚህ ላይ ነው ... "

(ወ.ጊ. ግንቦት 5/47)

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ይህችን ቃል የተናገሩት፣ ጉዞአቸውን ወደ አሩሲ ለመቀጠል ከአዲስ አበባ ሲነሡ፣ ሊሰናበቷቸው እቤታቸው ለመጡት የቅርብ ወዳጆቻቸው ለሆኑ ሰዎች ነው። ጸሐፊ ትዕዛዝ! እውነታቸውን ነው። የደረሰባቸው፣ ያላሰቡትና ያልጠበቁት በመሆኑ፣ መቀበሉ ቀላል አልነበረም። ይሁን እንጂ፣ በዚህ ዓለም በከፍተኛ የመንግሥት አስተዳደርና በፖለቲካ መሪነት የተሰለፉ ሰዎች፣ እንደ አጀማመራቸው መጨረሻቸው የተሳካላቸው በጣም ጥቂቶች ናቸው። የጀመሩት ረዥም ጉዞና ያደረጉት ዕቅድ ደግሞ በድንገት የሚጨልምባቸውም ጥቂቶች አይደሉም። ይህም ቢሆን፣ በፖለቲካው ዓለም አንድ ቀን ተመልሰው ብርሃን የማየት ዕድል እንደሚኖራቸው ተስፋ በማድረግ የሚታገሉት ብዙዎች ናቸው። በእኛ ትውልድ ደርሰን ያየናቸው አጅሬ ወልደጊዮርጊስም፣ ምንም እንኳ ተመልሰው ሲመጡ ባናያቸውም፣ በአንድ ወቅት ተመልሰው እንዲመጡ ሙከራ ተደርጐ እንደነበረ የምናውቅ ጥቂቶች አይደለንም። የሆነ ሆኖ በዚህ ተለዋዋጭ በሆነው የፖለቲካ ዓለም፣ ሰው ሁሉ በሚያደርገው ጥረት፣ ክፉም ሆነ ደግ ነገር ሳይደርስበት ሕይወቱን የፈጸመ የለም። ወልደጊዮርጊስም ከእነዚሁ አንዱ ናቸው።

ዓርብ ግንቦት 5 ቀን 1947 ዓ.ም የመጨረሻው ስንብት በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት በተከናወነበት ዕለት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ንጉሠ ነገሥቱን ሲሰናበቱ፣ " ... ጃንሆይ እንዲያምኑኝ እየለመንኩ፣ ከምናፍቀው ፊትዎ ስለይና ስሰናበትዎ፣ ከፍ ያለ ሐዘን ይሰማኛል። በሌላ በኩል ደግሞ፣ ፈቃድ ፈጻሚ በመሆኔ ደስ ይለኛል .... " ሲሉ ተናገሩ። ጃንሆይ ይህንን ከጸሐፊ ትዕዛዝ የቀረበላቸውን መልካም ስሜት ካዳመጡ በኋላ፣ የመጀመሪያው ጥያቄያቸው፣ መቼ ለመሄድ ነው ያሰብከው? የሚል ነበር። ወልደጊዮርጊስም የጌታቸውን ጠባይ ደህና አድርገው ስለሚያውቁ፣ የሚደሰቱበትን እንጂ፣ ቅር የሚሰኙበትን መልስ አልሰጧቸውም። " ... ነገ ቅዳሜ ግንቦት 6 ቀን ጠዋት ከአዲስ አበባ ተነሥቼ ማታውኑ ከጠቅላይ ግዛቱ ዋና ከተማ አሰላ ገብቼ ለማደር ተዘጋጅቻለሁ ... " አሏቸው። በዚህ ጊዜ፣ የጃንሆይን የፈገግታ ገጽ ሲያዩ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ በልባቸው ያሰቡትን መግለጽ ፈለጉ። " ... ጃንሆይ! እንደገና ለመተያየት ዕድሌ በእግዚአብሔር እጅ ስለሆነ፣ የዛሬን ተዝናንቼ አንድ የከነከነኝን ነገር ለመግለጥ እንዲፈቅዱልኝ እለምናለሁ ... " አሉ። ንጉሠ ነገሥቱም ፈቀዱላቸው። " ... የጃንሆይን ትዕዛዝ ለመፈጸም በመዘጋጀቴ እጅግ ደስ ሲለኝ፣ የተሾምኩ ዕለት በዱክ ቤት በአቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ ዛሬ ምክትል ጸሐፊ ትዕዛዝ የተነበበልኝ ወቀሳ፣ አዕምሮዬ ላይ ተቀርፆ ማዘን ብቻ ሳይሆን ሰላምም ነሥቶኛል። ጃንሆይ



ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከተሾሙ በኋላ ወደ አሩሲ (ዛሬ አርሲ) ጉዞአቸውን ማፋጠናቸው የተወደደ ሆኖላቸዋል።

በሚመስልም እንድታረም ያደርጋሉ እንጂ፤ ይህንን የመሰለ ሞራልን የሚገድል ቅጣት እንዲደርስብኝ የሚፈልጉ አለመሆንዎን ከእኔ ከራሴ ይበልጥ የሚያውቅ የለም። በዚሁ የዱክ ቤት ወቀሳው ከወረደብኝ በኋላ፤ ለጠቅላይ ሚኒስትሩ ለቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው " ... ይህ የተነገረው ቃል የእናንተ በመሆኑ ልቤ አይቀበለውም። እኔም እንደእናንተው የጃንሆይ ታማኝ አገልጋይ ነኝ። የትናንቱ ዕምነቴ ዛሬም ሆነ ነገ አይለወጥም ... " ብዬ ሐሳቤን ገልጬላቸዋለሁ። አሁን ይህ ሁሉ ያለፈ ታሪክ ሆኗል። ነገር ውሉ ካደረ፤ እንዲያውም ከሰነበተ፤ ከእሳትነቱ ወደ መክሰሙ ይሸገራል። እኔም የዕድሌን ተቀብያለሁ። ነገር ግን ከእንግዲህ ወዲህ ጃንሆይ ማንንም ሰው እንዳያምኑ አደራዬን ማጥበቅ እወዳለሁ። ሰው ለራሱ እንጂ ለሌላ አያስብም። ይህንን የምናገረውም ምልክት ስላለኝ ነው .... " በማለት ንግግራቸን ፈጸሙ።

ንጉሠ ነገሥቱ ይህንን አስተያየት ካዳመጡ በኋላ፤ ምንም እንኳ በየጉዳዩ ላይ ለመነጋገር አለመፈለጋቸውን ቢያሰሟቸውም፤ ወልደጊዮርጊስ አፍነው ይዘውት የነበረውን ሁሉ አውጥተው ለማስረዳት በመቻላቸው ተደስተዋል። በዚህ በግንቦት 5 ቀን 1947 ዓ.ም ጸሐፊ ትዕዛዝ ጃንሆይን ለመሰናበት ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት የቀረቡትና፤ በማግሥቱም ጠዋት ጉዞአቸውን ወደ አሰላ ለመቀጠል የተዘጋጁት፤ ከደረሰባቸው ብስጭት ሙሉ በሙሉ ከተላቀቁ በኋላ ነው ባይባልም፤ ብዙ ጥረት በማድረግ መንፈሳቸው ቅን እንዲያስብ አድርገው ነው ማለት ይቻላል። ንጉሠ ነገሥቱም ዋና ረዳታቸው የነበሩትን ሰው፤ በአንድ ጊዜ ከዚያ ከትልቁ ሥልጣን ሲያነሷቸውና ሲያርቋቸው፤ ምን ያህል ቅሬታና ብስጭት እንደሚያድርባቸው ደህና አድርገው ስለሚያውቁ፤ በዚህ በግንቦት 5 ቀን የተቀበሏቸውና ያነጋገሯቸው በመልካም መንፈስ ነበር ማለት ይቻላል። በመጨረሻም ሲያሰናብቷቸው፤ "በመንገድህ እግዚአብሔር ይከተልህ" ብለው በመመረቅና ጸሐፊ ትዕዛዝም እንደ ድሮአቸው ጫማ ለመሳም ወደ መሬት ዝቅ ሲሉ፤ ጃንሆይ አንገታቸውን ቀና አድርገው በመሳም ነው።

አዲሱ የአሩሲ ጠቅላይ ገዢ ቅዳሜ ግንቦት 5 ቀን 1947 ዓ.ም ጠዋት፤ በመንበረ ጸባኦት ቅድስት ሥላሴ ቤተክርስቲያን ካስቀደሱ በኋላ፤ በላንድ ሮቨር ጉዞአቸውን ወደ አሰላ ሲቀጥሉ፤ ምንጊዜም ያልተለይዋቸው ጽኑ ወዳጆቻቸው እነ ፊታውራሪ ፀሐዬ እና ተስፋዬ እንቁሥላሴ ከነቤተሰቦቻቸው ከአዲስ አበባ ውጭ አቃቂ እስከሚባለው ቦታ ድረስ ሄደው ሸኟቸው። ሌሎቹ ግን በጣም ብዙዎቹ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወዳጆች ናቸው እየተባሉ ዝናቸው ይነገርላቸው የነበሩት ሁሉ፤ እንኳንስ በመሸኘቱ፤ በሹመቱም ዕለት ብቅ አላሉም።

ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ የፖለቲካ ታሪካቸውን የያዘው ትልቁ ምዕራፍ ከተዘጋበት ከሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም ጀምሮ፤ ወደ አዲሱ ሥራቸው እስከሄዱበት ጊዜ ድረስ፤ አዲስ አበባ የቆዩት አሥራ ዘጠኝ ቀናት ብቻ ነው። በልማዱ፤ አንድ አገረ ገዥ ከተሾመ በኋላ፤ እጅግ አስቸኳይ ነገር ከሌለ፤ ለስንቅ ዝግጅትና ለጓዝ ማንሻ በሚል ሰበብ ከሁለት እስከ ሦስት ወራት አዲስ አበባ ይከርማል። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ግን ከተሾሙ ሐያ ቀናት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፤ አዲሱ ግዛታቸው ላይ ተገኝተው ሥራቸውን ተረክበዋል። እርግጥ ነው! ጸሐፊ ትዕዛዝ እስከዚህ ተጣድፈው መሄድን የመረጡት ትእዛዝ ደርሶአቸው አይደለም። የእሳቸው ከሹመታቸው በኋላ አዲስ አበባ መቆየት የሚወደድ አለመሆኑን ስለሚያውቁት፤ ሳይቀደሙ ቀድመው መገኘትን ስለመረጡ ነው።